# የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት

## የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ ከነገሡ በኋላ፤

የፋሽስት ጣልያን ወረራ፣

የሊግ ኦፍ ኔሽን ዳኝነት

የእንግሊዞች ነፃ አውጭነትና
የሞግዚት አስተዳደር፣

የስዌዝ ካናል ምሥጢራዊ ጉዞ
ቀ.ኃ.ሥ ከሩዝቬልት ጋር

## ከእንግሊዞች በኋላ፤

የመኰንን ሀብተወልድና
የወልደጊዮርጊስ አነሳስ፣

የሁለቱ ሰዎች ወዳጅነትና
የሥልጣን ትብብር

የወልደጊዮርጊስ የሥልጣን
ኃይልና የቤተመንግሥቱ
ሥጋት፣ .... መጨረሻው?



1ኛ መጽሐፍ – እንደ ኢት.አቆ 1923-1948
እ.ኤ.አ 1930-1955

ዘውዴ ረታ

**LAXMI PUBLICATIONS (P) LTD**

NEW DELHI, INDIA • BOSTON, USA

# ማውጫ

# ክፍል ፩

## የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ የመጀመሪያዎቹ አምስት ዓመታት

# ክፍል ፪

## ጥቁር ዳመና በኢትዮጵያ ፀሐይ

# ክፍል ፫

## የፈረደባት ኢትዮጵያ ለሰባት ወራት

ገጽ

# ክፍል ፬

## አውሮፓ ወደ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት

## የኢትዮጵያ ዕድል ምን ይሆን?

ገጽ

# ክፍል ፭

## የተበደለች ኢትዮጵያ ጸሎቷ ተሰማ

ገጽ

# ክፍል ፲

## የእንግሊዞች ዘመን

ገጽ

# ክፍል ፺

# የመኰንን ሀብተወልድ
# እና
# የወልደጊዮርጊስ ወ/ዮሐንስ
# አነሳስና የሥልጣን ዘመን

# ክፍል ፰

## ታሪካዊው የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የሥልጣን ፍጻሜ

# ይድረስ ለአንባቢዎቼ

እ.ኢ.ት.አቆ. ግንቦት 26 ቀን 1997 ዓ.ም (03/06/05) "ተፈሪ መኮንን" የተሰኘውን መጽሐፍ አዘጋጅቼ ባቀረብኩላችሁ ዕለት፣ በሚቀጥለው ጊዜ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ ጽፌ ለማንበብ እንደምትችሉ የሰጠሁትን ቃል አስታውሳለሁ። በዚህ መሠረት፣ እ.ኢ.ት.አቆ. ከ1923 ዓ.ም እስከ 1948 ዓ.ም ድረስ ያለውን የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ የመጀመሪያውን ክፍል አዘጋጅቼ ሳቀርብላችሁ ከፍ ያለ ደስታ ይሰማኛል።

ይህንን የሀያ አምስት ዓመታት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ታሪክ በምጽፍበት ባለፉት ስድስት ዓመታት ውስጥ፣ የጤና ችግር ገጥሞኝ ጊዜ ቢወስድብኝም፣ የእግዚአብሔር እርዳታና ምህረቱ ሳይለየኝ ያሰብኩትን ለመፈጸም በመቻሌ፣ ለፈጣሪያችን የማቀርበው ምሥጋና ወሰን የለውም። ከአንባቢዎቼም መካከል ብዙዎቻችሁ ይህንን ታሪክ እንድጽፍ ያተጋችሁኝና የሞራል እርዳታችሁ ያልተለየኝ በመሆኑ፣ የታሰበው ከግቡ ደርሶ ስታገኙት እንደምተደሰቱ ተስፋ አደርጋለሁ።

እንድታነቡት ያቀረብኩላችሁ ይህ መጽሐፍ፣ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት ውስጥ የሀያ አምስቱን ዓመታት ብቻ የሚተርክ ነው ሲባል፣ ምናልባት ለአንዳንዶቻችሁ ብዙዎቹን ጉዳዮች ያላሟላ የአጭር ዘመን ታሪክ መስሎ ይታያችሁ ይሆናል። ነገር ግን፣ በእነዚህ በሀያ አምስት ዓመታት ውስጥ የተካሄዱት የኢትዮጵያ ታሪኮች እጅግ ብዙዎች በመሆናቸው፣ ከእነዚሁ ውስጥ ዋና ዋናዎቹ ጉዳዮች ተመርጠው የታተሙት ይኸው እንደምታዩት ስምንት መቶ ገጾች ወስደዋል።

አንዳንድ ሰዎች እንደአሳሰቡኝ፣ የአርባ አምስቱን ዓመታት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን መንግሥት ሙሉውን ታሪክ በአንድ ትልቅ መጽሐፍ አጠቃልሎ ለማተም ቢሞከር፣ ብዛቱ እጅግ ቢያንስ እስከ አንድ ሺህ ሦስት መቶ ገጾች እንደሚደርስ ተገምቷል። ከዚህ በላይ ደግሞ ይህንን የሚያህል ግዙፍ መጽሐፍ ለማሳተሚያውና ለጥራዙ የሚያስፈልገው የገንዘብ ወጭ ብዙ ስለሆነ፣ መጽሐፉን ለአንባቢዎች እንዲዳረስ ለማድረግ ጨርሶ የሚቻል ሆኖ አልተገኘም። ስለዚህ፣ የታሪኩን ዘመን በሁለት ክፍሎ ለአንባቢዎች በሚመች መልክ አሳትሞ ማቅረቡ የተሻለ አማራጭ መሆኑ በብዙ ጥናት ስለተደገፈ፣ እነሆ ይህ የመጀመሪያው የሀያ አምስት ዓመታት ታሪክ፣ በስምንት ዋና ዋና ክፍሎችና በሰባ ሦስት ምዕራፎች ተደልድሎ ቀርቦላችኋል።

በዚህ ታሪክ ውስጥ የኢትዮጵያ ሕዝብ እንዲያውቃቸው እጅግ አስፈላጊ ናቸው የተባሉት ዋና ዋና የሆኑት ቁም ነገሮች ተተንትነው እንዲቀርቡ ብርቱ ጥረት ተደርጓል። ብዙዎች ኢትዮጵያውያኖች እንደሚያውቁት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በንጉሠ ነገሥትነት አገራችንን በመምራት በቆዩበት በአርባ አራት ዓመታት ዘመን ውስጥ፣ ብዙ ፈተናና መከራ ያሳለፉ መሆናቸው የሚዘነጋ አይደለም።

ጥቅምት 23 ቀን 1923 ዓ.ም ተፈሪ መኮንን "ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ" ተብለው የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ በመሆን ሥርዓተ ንግሣቸውን ባከበሩ ማግሥት፣ የመጀመሪያዎቹ እርምጃዎቻቸው ምንና ምን እንደነበሩ ማስታወስ ያስፈልጋል። እነዚህም አንደኛ፣ የኢትዮጵያን አስተዳደር ከፍጹም ፈውዳላዊ ሥርዓት ለማላቀቅና ወደተሻለ አመራር ለማሸጋገር የሚያስችል ሕገ መንግሥትን ማቆም ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ፣ ለሕዝቡ ሥልጣኔ መሠረት የሆነውን ዘመናዊውን የትምህርት ብርሃን፣ በመላ ኢትዮጵያ መዘርጋት ነበር። ይህንንም ዓላማቸውን ከግብ ለማድረስ በሚያደርጉት ጥረት፣ ለንግሥ በዓላቸው ተካፋዮች ሆነው ወደ አዲስ አበባ እንዲመጡ የጋበዟቸው፣ የአውሮፓና የአሜሪካ መንግሥታት እርዳታ እንደሚለግሷቸው ከፍ ያለ ተስፋ አድርገው ነበር። ነገር ግን በክብር ተጋብዘው አዲስ አበባ የመጡት የታላላቆቹ መንግሥታት እንደራሴዎች፣ ዓይናቸው ያተኮረውና አስተያየታቸው ያዘነበለው፣ ኢትዮጵያ ከሠለጠነው ዓለም እጅግ ርቃ መገኘቷና ፍጹም ፈውዳላዊ በሆነ አስተዳደር የተያዘች በመሆኗ፣ በሥልጣኔ በተራመደው በዓለም ቤተሰብ ውስጥ የነፃ መንግሥትነት መብት ሊኖራት አይገባም በሚል አስተሳሰብ ላይ የተመሠረተ ሆነ። በዚህም አኳኋን፣ የታላላቆቹ አገሮች እንደራሴዎች ከአዲስ አበባው ጉብኝታቸው ሲመለሱ፣ አብዛኛዎቹ ለየመንግሥታቸው ባቀረቡት ራፖር፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንደተመኙት እንኳንስ ለኢትዮጵያ ዕድገት ዕርዳታ ለመለገሥ ይቅርና፣ ለነፃነቷም ዋስናት የሚያጠራጥር ሁኔታ የሚያሣይ ሆነ። በተለይም የጣልያኑ መልዕክተኛ ልዑል ፈርዲናንዶ ወደ አገሩ ወደ ሮማ ሲመለስ፣ ለፋሽስቱ መሪ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ በጻፈው ራፖር፣ የዱቼን የቅርብና የሩቅ ዓላማ ለመደገፍ " ... ብቻዋን ከጭለማው ዓለም ለመላቀቅ ምንም ተስፋ የሌላት ኢትዮጵያ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ከሠለጠኑት አገሮች እኩል አባል ሆና መኖር የምትችለው እስከ መቼ ነው? ... " የሚል ጥያቄ አቅርቧል።

እንግዲህ! ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ኢትዮጵያን ወደ ዘመናዊ ሥልጣኔ ለመምራት ቆርጠው መነሳታቸውን ታላላቆቹ መንግሥታት እንዲያውቁላቸውና እንዲረዷቸው ያደረጉት ተስፋ ባይሳካም፣ አገሪቱ ባላት አቅም የሚችሉትን ሁሉ ከመፈጸም ወደ ኋላ አላሉም። በነገሡ በዓመቱ በኢትዮጵያ የብዙ ሺህ ዓመታት ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ ሕገ መንግሥት ተዘጋጅቶ በሥራ ላይ ዋለ። የትምህርት ሚኒስቴርም ተግባርና ኃላፊነት ከሌሎቹ ሚኒስቴሮች ሁሉ የበለጠ እንዲሆን

ቀደምትነት ተሰጠው። "ልጁን ያላስተማረ እራሱን እንደመግደል የሚያስቆጠር ነው" ተብሎ የተሰጠውን የንጉሠ ነገሥቱን መምሪያ፣ ወላጆች ሁሉ እየተከተሉ ልጆቻቸውን ወደ ተማሪ ቤት በብዛት መላክ ጀመሩ።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትነትን ሥልጣን በተቀበሉ በአራተኛው ዓመት፣ የጣልያን ፋሽስት መሪ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ራሱ የፈጠረውን የወልወል ግጭት የጠብ መጫሪያ በማድረግ፣ ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ባዘጋጀው የጦር ኃይል በኢትዮጵያ ላይ ጦርነት አውጆ፣ አገራችንን መውረር ጀመረ። በዚህ ጊዜ የዠኔቩ የመንግሥታት ማህበር፣ የተመሠረተበትን ዓላማ ተከትሎ የአጥቂውን ጥፋተኛነት በማረጋገጥ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስከበር አስፈላጊውን እርምጃ መውሰድ ነበረበት። ነገር ግን በዚያን ዘመን የሊግ ኦፍ ኔሽን ጥቅም የፋሽስቱን መሪ መደገፍና የአውሮፓን ደህንነት መጠበቅ ስለሆነ፣ ሙሶሊኒ በኢትዮጵያ ላይ ያጠመደው ያ ሁሉ ዘመናዊ መሣሪያ ሳይበቃው ቀርቶ፣ በዓለም ሕግ በተከለከለው በጋዝ ጢስና በመርዝ ሕዝቡን ሲያቃጥል፣ ታሪከኛው የመንግሥታት ማኅበር ድምጹን አጥፍቶ ዝም አለ። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ለአምሳ ስድስቱ መንግሥታት የሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎች በዠኔቩ ሸንጐ ላይ ተገኝተው፣ "የዓለም ሕግ ተጥሶ ዛሬ በኢትዮጵያ ላይ የደረሰው ግፍ ነገ በሌሎቻችሁ ላይ ሊደርስ እንደሚችል አይታያችሁም ወይ? ... " ብለው ላቀረቡት የፍርድ ጥያቄ፣ ትክክለኛውን መልስ የሚሰጣቸው ሳያገኙ ቀሩ። በመጨረሻው፣ "እግዚአብሔርና ታሪክ ፍርዳችሁን ሲያስታውሱት ይኖራሉ" የሚል ትንቢታዊ ማስጠንቀቂያ ሰጥተው፣ በእንግሊዝ አገር መራራውን የስደት ሕይወት በጀመሩ በአራተኛው ዓመት፣ የኢትዮጵያ ደመኛ የሆነው ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር አብሮ በትናንት ወዳጆቹ በፈረንሣይና በእንግሊዝ አገሮች ላይ ጦር አሰልፎ ዘመተባቸው። በዚህ ጊዜ እንግሊዞች፣ በኢትዮጵያ ላይ የሰፈረውን የፋሽስት ጦር ማስለቀቅ ግዴታ ስለሆነባቸው፣ በወሰዱት እርምጃ የጥንታዊቷን የንግሥተ ሳባን አገር ነፃነት እቦታው ለመመለስ ፍላጐት ያደረባቸው መሰለው ታዩ።

እንደተባለውም፣ በታላቋ ብሪታንያ ጦር ኃይልና በአርበኞቻችን ብርቱ ተጋድሎ ፋሽስት ከተባረረ በኋላ የኢትዮጵያ ነፃነት ተመለሰ ሲባል፣ እንግሊዞች በታወቀው የተንኮል ጥበባቸው፣ በዘመኑ የሚካሄደው የዓለም ጦርነት ተፈጽሞ የሠላም ጉባኤ እስኪደረግና ጠቅላላ ውሣኔ እስኪሰጥ ድረስ፣ ኢትዮጵያ የጣልያን ኮሎኒ ሆና መቆጠር አለባት። ስለዚህም በጣልያን ፋንታ አስተዳዳሪዋ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ነው የሚል መግለጫ አወጡ። ይህንን ውሳኔ ያደረጉት የእንግሊዝ ወታደራዊው ባለሥልጣኖች ሲሆኑ፣ ዋናዎቹ መሪዎች የጦር ካቢኔው ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን፣ በተደረገው ውሳኔ መስማማታቸውን የሚያመላክት መረጃ አልነበረም። በዚህ እንግሊዞች በኢትዮጵያ ላይ የወሰዱት ያልተጠበቀ እርምጃ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን

እጅግ ያሳዘናቸው ከመሆኑም በላይ፤ ምን ማድረግ እንደሚቻል መንገዱ ሁሉ የተወሳሰበ ሆኖባቸው ነበር።

ደማቸውን እያፈሰሱ ከእንግሊዞች ጐን ሆነው ለኢትዮጵያ ነፃነት በታላቅ ጀግንነት የተዋጉት አርበኞቻችን፤ በጠላታችን በጣልያን ቦታ እንግሊዞች ተተክተው እንግዛችሁ የሚሉን ከሆነ፤ ከጫካችን ለምን ወጣን? ሲሉ ላቀረቡት ጥያቄ መልስ መስጠቱ ለጃንሆይ ቀላል አልነበረም። እንግሊዞች ባላቸው የጦር ኃይል መላ ኢትዮጵያን ተቆጣጥረው ይዘዋል። መሣሪያውም ገንዘቡም በእጃቸው ስለሆነ፤ የፈለጉትን ሁሉ ከማድረግ ማንም ሊያግዳቸው አልቻለም። ስለዚህም፤ ለንጉሠ ነገሥቱ ያላቸው አማራጭ፤ በከፍተኛ ትዕግሥት ከእንግሊዞቹ ወታደራዊ ባለሥልጣኖች ጋር መደራደርና መስማማት ብቻ ሆነ። ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ኤደን ንጉሠ ነገሥቱ መልዕክት ማስተላለፍ የሚችሉት፤ በእንግሊዞች ከፍተኛ ቁጥጥር በሚካሄደው የመገናኛ መስመር ብቻ ስለሆነ፤ የሚያስቡትን ለመግለጽና የሚፈልጉትን ለመጠየቅ አልቻሉም። በዚህ ምክንያት፤ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴና በእንግሊዞች መካከል የተፈረመው የመጀመሪያው ውል (1942-1944) ወታደራዊው ባለሥልጣን በፈለገው ዓይነት ኢትዮጵያን በሞግዚት አስተዳደር መልክ ይዞ የሚያቆያት ሆነ። በዚህ አኳኋን የአገራችን አስተዳደር ሥልጣን በእንግሊዞች እጅ ሆኖ ለሁለት ዓመት ከቆየ በኋላ፤ አስቸጋሪው ዘመን ሲፈጸም፤ ለሁለተኛው ስምምነት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ሚኒስትሮቻቸው ያደረጉት የዲፕሎማሲ ጥረት አንድ ዓይነት ውጤት አስገኘላቸው። ይኸውም ቸርችልና ኤደን በጉዳዩ ገብተው፤ ወታደሮቹን ከሥልጣን እንዲርቁ በማድረጋቸው፤ ለሁለተኛ ጊዜ የተፈረመው ውል ከመጀመሪያው የተሻለ ሆነ። ሆኖም ሁለተኛው ስምምነት የተፈረመው ለሁለት ዓመታት ጊዜ ነው ቢባልም፤ የኢትዮጵያ ነፃነት ሙሉ በሙሉ የተረጋገጠ መሆን አልቻለም ነበር። ስለዚህም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ብዙ ጥረት አድርገው እ.ኤ.አ በየካቲት 1945 ዓ.ም በስዌዝ ካናል የአሜሪካውን መሪ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልትን አግኝተው በአገራቸው አስተዳደር ላይ ስለአጋጠማቸው ችግር በሰፊው በማነጋገራቸው፤ እንግሊዞች በኢትዮጵያ መንግሥት ላይ የሚያደርጉትን ጫና ለማላቀቅ አስቻላቸው።

እንግዲህ! ማንም ሰው በቀላሉ እንደሚረዳው፤ ኢትዮጵያ የነፃነት ችግር ያጋጠማት በሁለት ኮሎኒያሊስት በሆኑ አገሮች ነው። የመጀመሪያው የፋሽስቱ የሙሶሊኒ የግፍ ወረራ ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ ነፃ አውጭዎች ነን ብለው በመጡት ወዳጆቻችን በምንላቸው በእንግሊዞች ወታደራዊ የሞግዚት አስተዳደር የተፈጸመብን በደል ነው። ከእነዚህ ከሁለቱም ኮሎኒያሊስቶች፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስመለስ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት የደረሰበት መከራና ፈተና በቀላሉ የሚገመት አይደለም። ይህን ሁሉ በተለይ አዲሱ ትውልድ እንዲያውቀው ስለሚያስፈልግ፤ በዚህ መጽሐፍ ውስጥ ታሪኩ በተቻለ መጠን ተዘርዝሮ ቀርቦለታል።

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በፋሽስት ጣልያን የተገፈፈውን የኢትዮጵያን ነፃነት ካስመለሱና፤ ከዚያም እንግሊዞች የጫኑባቸውን የሞግዚት አስተዳደር ቀንበር ካስለቀቁ በኋላ፤ ለአገሪቱ የውስጥ አመራር ሁለት ዋና ዋና የሆኑ ሰዎችን መርጠው ከፍተኛ ሥልጣን ሰጧቸው። እነዚህም ሰዎች፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ እና አቶ መኰንን ሀብተወልድ ናቸው። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ እነዚህን ሁለት የደሐ ወገኖች የሆኑትን ሰዎች መርጠው የቅርብ ረዳቶቻቸው እንዲሆኑና ከሙሉ ሥልጣን ጋር እንዲሠሩ ሲያደርጉ፤ ይህ ሐሳብ በመሳፍንትና በመኳንንት ዘንድ የተደገፈ አልሆነም። ጃንሆይ ግን፤ እነዚህን ሰዎች የመረጧቸውና ከፍተኛ ሥልጣን በመስጠት ያቀረቧቸው፤ በችሎታቸውና በጥንካሬያቸው ሙሉ ዕምነት በማሳደር ነበር። ነገር ግን፤ በመሳፍንትና በመኳንንት ዘንድ የንጉሠ ነገሥቱ እርምጃ ያልተወደደው፤ ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ የጌቶችና የድሆች ወገን እያሉ የሚከፋፍሉና በተለይም ለመሳፍንትና ለመኳንንት አክብሮት የሌላቸው ናቸው በመባል ነው። ነገር ግን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ይህንን ሐሳብ አልተቀበሉትም። ታማኞቼ ናቸው ብለው የመረጧቸውን ወልደጊዮርጊስንና መኰንን ሀብተወልድን በከፍተኛ ሥልጣን ላይ ደልድለው፤ የመንግሥታቸው አመራር ለብዙ ዓመታት እንዲቀጥል አደረጉ።

እነዚህ ሁለት የንጉሠ ነገሥቱ ባለሟሎችና ከፍተኛ ባለሥልጣኖች፤ ከምን ተነስተው እዚህ ደረጃ ለመድረስ እንደበቁና የነበራቸውም የሥልጣን ትብብርና ኃይል እስከምን ድረስ እንደዘለቀ፤ በመጨረሻም የወልደጊዮርጊስ ኃይል ለብቻው እያስጋ ሲመጣ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሁለቱን ሰዎች አንድነት በመለያየትና፤ አንዱን አቆይቶ ሌላውን ከሥልጣን በማንሳት የወሰዱት እርምጃ በምን አኳኋን እንደተፈጸመ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ ለማወቅ ያደረበትን ብርቱ ጉጉት በግልጽ ስለተረዳሁ፤ ረዥም ጊዜ ወስጄ፤ እውነተኛውንና ትክክለኛውን ታሪክ በዝርዝር ለአንባቢዎቼ አቅርቤያለሁ።

## የተወደዳችሁ አንባቢዎች

በጠቅላላው በዚህ "የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት" በተሰኘው መጽሐፍ ውስጥ የተገለጹትን ታሪኮች ገና በወጣት ዕድሜ ላይ ከነበርኩበት ዘመን ጀምሮ በብዙ ስከታተለውና ሳጠናው የቆየሁበት ጉዳይ መሆኑን፤ ለአንባቢዎቼ መግለጽ እወዳለሁ። እኔው ራሴ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመን የገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ጋዜጠኛ ሆኜ በሠራሁበት ጊዜ፤ በንጉሠ ነገሥቱ አካባቢ ሲከናወኑ በዓይኔ ያየኋቸውን ከፍተኛ የሆኑ ጉዳዮችንና ከአዋቂዎቹም ሲነገሩ በቀጥታ የሰማኋቸውን ሁሉ በማስታወሻዬ ላይ መዝግቤያቸው ስለነበረ፤ ዛሬ ለጻፍኩት የታሪክ መጽሐፍ በጣም ረድተውኛል። ኋላም ከንጉሠ ነገሥቱ ዋና ዋና ሚኒስትሮችና ታላላቅ ሰዎች

ዘንድ የመቅረብ ዕድል ስለነበረኝ፣ እነሱን በማነጋገርና ቃለ መጠይቅ በማድረግ፣ ስለ ቀ.ኃ.ሥ ካቢኔ ሥራ አመራርና በተለይም በመንግሥት ላይ ስለደረሱት ችግሮች እውነተኛውን ታሪክ ለመሰብሰብ ችያለሁ። ቀጥሎም በአሜሪካና በእንግሊዝ፣ በፈረንሣይና በጣልያን አገሮች ተዘዋውሬ ስለ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት የተጻፉትን የዲፕሎማቲክ ኮሬስፖንዳንሶች ሁሉ በዝርዝር አጥንቻለሁ። በተጨማሪም ኢትዮጵያ በፋሽስት በተወረረችበት ጊዜ፣ ጉዳዩ በመንግሥታት ማህበር ሸንጐ ላይ በምን መልክ እንደታየና ኢትዮጵያም ምን ያህል ተሚግታ ፍርድ እንደተነፈጋት ዤኔቭ ሄጄ፣ የቀድሞዎቹን የሊግ ኦፍ ኔሽን ቤተመዛግብት በመመርመር ጠቃሚዎቹን ሰነዶች ሰብስቤያለሁ።

እንግዲህ! ይህ የታሪክ መጽሐፍ የተዘጋጀው፣ ትክክለኛ በሆኑ ሰነዶችና ከታወቁ ታላላቅ ሰዎች በተገኙ መረጃዎች ላይ ተመርኩዞ ስለሆነ፣ ከልብ ወለድና ከአፍ ታሪክ ነፃ መሆኑን አንባቢዎቼ እንዲገነዘቡልኝ አሳስባለሁ። ሆኖም ባቀረብኳቸው ታሪኮች ውስጥ፣ ይህ ጐድሏል፣ ይህ ቀርቷል፣ የሚባሉ ጉዳዮች ሊኖሩ እንደሚችሉና እንደሚኖሩም ደህና አድርጌ አውቃለሁ። ለምሳሌም ያህል፣ ከፋሽስት ጣልያን ጋር በተደረገው ተጋድሎ፣ የአርበኞቻችንን የጀብዱ ታሪክ ዘርዝሬ ለመጻፍ አልተመቸኝም። እንደሚታወቀው የዚህ መጽሐፍ ዓላማና ግብ፣ በንጉሠ ነገሥቱ የፖለቲካና የመንግሥት አመራር ላይ የተመሠረተ ስለሆነ፣ የጀግኖቻችንን ጉዳይ በስፋት ለመጻፍ ባለመቻሌ ከፍ ያለ ይቅርታ እጠይቃለሁ። በመሠረቱ የኢትዮጵያ አርበኞችና ጀግኖች ታሪክ ራሱን የቻለ አንድ ትልቅ መጽሐፍ የሚወጣው ስለሆነ፣ ወደፊት እኔም ሆንኩ ሌሎች ጸሐፊዎች አስፈላጊውን እንደምንፈጽም ተስፋ አደርጋለሁ።

መልካም ንባብ ይሁንላችሁ
ዘውዴ ረታ

# ክፍል ፩

# የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ የመጀመሪያዎቹ አምስት ዓመታት

እንደ.ኢት.አቆ 1923 - 1928
እ.ኤ.አ 1930 - 1935

# ክፍል ፩

## የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ

ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ምኒልክ በነገሡ በዐሥራ ሦስት ዓመት ከስድስት ወር፣ በተወለዱ በሃምሳ ሦስት ዓመት ከዐሥራ አንድ ወር፣ ከዚህ ዓለም በሞት በተለዩበት ቀን፣ ሳይውል ሳያድር መሳፍንትና መኳንንት ወዲያውኑ ተሰብስበው በሰጡት ውሳኔ መሠረት፣ አልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን ከዚሁ ዕለት ጀምሮ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መሆናቸው ለሕዝቡ በአዋጅ ተነገረ።

ይህ ውሳኔ ለሕዝቡ ከተገለጸ በኋላ፣ አዲሱ የምኒልክ ሥልጣን ወራሽ፣ የንግሥቲቱ ቀብር ከመፈጸሙ በፊት፣ ለመላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ባስነገሩት አዋጅ፣ « .... ሰው ሆኖ ከሞት የሚቀር አለመኖሩ የታወቀ ቢሆንም፣ ንግሥተ ነገሥታት እናታችን በጥቂት ቀናት ሕመም በድንገት ስለተለዩን፣ በእኔና በመላው የኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ የደረሰው ኃዘን እጅግ የጠነከረ ነው። ይሁን እንጂ፣ የሕዝብ እረኛ የሆነው ንጉሥ ሲሞት፣ ንጉሥ መተካቱ የቆየ ልማድ ስለሆነ፣ እኔም በታጩሁበት በመንበረ ዳዊት ዙፋን ላይ ሆኜ፣ በእግዚአብሔር እርዳታ ሕዝቤን ለመጠበቅ ስለተዘጋጀሁ፣ ገበሬ እረስ ! ነጋዴ ነግድ ! ሠራተኛ ሥራ ! ከአባቶቼ ሲያያዝ በመጣው ደንብና ሕግ አሳድርሃለሁ። .... »* ሲሉ አስታወቁ። የንግሡ በዓል ግን በይፋ የሚከበረው፣ ከጥንት ሲያያዝ በመጣው ባህል መሠረት፣ ስለ ንግሥቲቱ ሞት በመላ ኢትዮጵያ የሚደረገው የስድስት ወራት ኃዘን ከተፈጸመ በኋላ፣ ጥቅምት 23 ቀን 1923 ዓ.ም እሑድ እንዲሆን ተወሰነ።

እንደሚታወሰው፣ ንግሥቲቱ ከመሞታቸው ከአንድ ዓመት ተኩል በፊት መስከረም 27 ቀን 1921 ዓ.ም አልጋወራሹ ራስ ተፈሪ መኰንን በያዙት ሥራ " ንጉሥ " ተብለው ዘውድ ጭነዋል። በዚያን ጊዜ፣ ይህ ዘውድ ለተፈሪ መኰንን የተሰጠው፣ ለአልጋወራሽነታቸው ደረጃ ሳይሆን፣ ለንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት እንደራሴነታቸው ከቀድሞው የበለጠ ሥልጣን እንዲያገኙ ለማድረግ ነበር። ይኸውም፣ በሌላ አነጋገር፣ ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ የአባ ዳኘው ምኒልክ የተወደደው ዘውድ ምልክትና የኢትዮጵያ ሕዝብ አንድነት የበላይ ጠባቂ ሲሆኑ፣ የመንግሥቱ አስተዳደር በሙሉ ሥልጣን የሚካሄደው፣ " ንጉሥ " ተብለው ዘውድ በጫኑት በአልጋወራሹ ብቻ ይሆናል ማለት ነው። በዚህ አኳኋን የንግሥቲቱ ኃላፊነት ወሰን ተደርጉለት የአልጋወራሹ የመንግሥት መሪነት ሥልጣን ከፍ እንዲል ማሕል ሠፋሪዎች* ያቀረቡትን ጥያቄ ዘውዲቱ ምኒልክ ለመቀበል ሲገደዱ፣ በአድራጐቱ እጅግ ማዘናቸውና መገረማቸው ለማንም የተደበቀ አልነበረም። ሆኖም ንግሥት ዘውዲቱ ምንም እንኳን ይህን የወታደሮች ዓድማ ያስነሡት ራሳቸው

---

* ከቤተመንግሥት ዜና መዋዕል የተገኘ

* የወታደሩ ክፍል

ተፈሪ መኰንን ናቸው ብለው ቢያምኑም፤ ከደግነታቸውና ከሰላማዊነታቸው የተነሣ፤ በአልጋወራሻቸው ላይ ያደረባቸውን ቅሬታ ሕዝቡ እንዲሰማ አልፈለጉም። ለአንዳንድ ታማኞቻቸው ታላላቅ ሰዎች እንደገለጹት፤ « .... **ወንድሜ አልጋወራሽ አገራችንን ለማስተዳደር ሥልጣኑ የኔ ብቻ ነው ብሎ ተነሥቶብኛል ብዬ ብናገር፤ ሕዝቡ በቁጭት ተነሥቶ ሽብር ሊፈጠርና አለአግባብ ደም ሊፈስ ይችላል። ስለዚህ፤ በእኔና በአልጋወራሽ መካከል ስምምነት ጠፍቷል ተብሎ የርስ በርስ ግጭት እንዳይፈጠር፤ ወንድሜ ራስ ተፈሪ "ንጉሥ " እንዲባል ዘውድ እሰጠዋለሁ** .... » ብለው ወሰኑ። እዚህ ላይ እንደሚታየው፤ ንግሥቲቱ አልጋወራሻቸው ዘውድ እንዲጭኑ ማሕል ሠፋሪዎች ዓድመው ያቀረቡላቸውን ጥያቄ የተቀበሉት እጅግ ከፍ ባለ ቅሬታ ቢሆንም፤ በዘውዱ አሰጣጥ በዓል ላይ፤ « .... **ንጉሥ ተፈሪ ለኢትዮጵያ ሕዝብና ለአገራችን ይጠቅማል ብሎ የሚሠራውን ሁሉ እግዚአብሔር ይባርክለት ! .... » የሚል ምርቃታቸውን አልነፈጓቸውም።**

ይህ ከተፈጸመ ከአንድ ዓመት ተኩል በኋላ፤ መጋቢት 24 ቀን 1922 ዓ.ም ንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ በጥቂት ቀናት ሕመም ከዚህ ዓለም በሞት በተለዩ ጊዜ፤ አልጋወራሹ ንጉሠ ነገሥት ለመሆን እጅግ ከመቸኮላቸው የተነሣ፤ በሐኪም መድኃኒት ሕይወታቸው በቶሎ እንዲያልፍ አስደርገዋል፤ የሚል ሐሜታ ተነዛባቸው። ስለዚሁ ጉዳይ፤ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ በአገር ውስጥም ሆነ በውጭ አገር ባደረገው ምርምር፤ ይህን ሐሜታ የሚደግፍ አንዳች የታመነ ምንጭ አላገኘም።

በዚያን ዘመን የተፈሪ መኰንን ወገኖች ካልሆኑትና ለንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ፍጹም ታማኞች ከነበሩት ዋና ዋና ሰዎች መካከል፤ የአፄ ምኒልክ ምሥጢር ጸሐፊ የነበሩት ቀኛዝማች ደሀኔ ወልደማርያም፣ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር የነበሩት ነጋድራስ ፀምሩ ገብረሥላሴ፣ ንግሥቲቱን ለዘጠኝ ዓመታት በጸሐፊነት ያገለገሉት አባቴ ቀኛዝማች ረታ ወልደአረጋይ፤ ሲጨዋወቱ እንደሰማሁት፤ **አልጋወራሹ ዘውዲቱ ምኒልክን በመድኃኒት አስገደሏቸው እየተባለ የሚነዛውን ወሬ አይቀበሉትም።**

እርግጥ ! እነዚህ ሰዎች አልጋወራሽ ተፈሪ በመስከረም 1921 ዓ.ም የማሕል ሠፋሪን ሠራዊት አሳድመው ንግሥቲቱን በማስገደድ "ንጉሥ " ተብለው ዘውድ መጫናቸውን ያወግዛሉ። በእነሱ አመለካከት፤ አባ መቻል ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ ከሞቱበት ከታህሣሥ 3 ቀን 1919 ዓ.ም ጀምሮ፤ ንግሥቲቱ የሚያማክሩት ተደማጭ ሰው በማጣታቸው፤ አልጋወራሹ እንደፈለጉ በሙሉ ሥልጣን እንዲሠሩ ከማድረግ በስተቀር፤ አንዳች ዕንቅፋት አልፈጠሩባቸውም ነበር። ስለዚህ፤ አልጋወራሹ ለሥልጣን ሲሉ በሩጫ ንጉሥ ከመባል፤ እግዚአብሔር የፈቀደላቸውን ቀን በትዕግሥት ቢጠብቁ ኖሮ፤ እናቴ የሚሏቸውን ንግሥታቸውን ወደ መጨረሻው ዘመናቸው ላይ ቅር ከማሰኘት ይድኑ ነበር፤ የሚል ዕምነት ያላቸው መሆኑ ታውቋል።

**እንግዲህ ! ከዚህ በላይ እንደተገለጸው የንግሥቲቱ ታማኞች በመድኃኒት ተገድለዋል የሚባለውን ካልተቀበሉት፤ በየቦታው የነፈሰው ወሬ ሁሉ መሠረት ያልጨበጠና ትክክለኛ መረጃ ያልቀረበበት ነው ከማለት በስተቀር ሌላ ምን ዓይነት ግምት ሊሰጠው ይችላል ? .....**

# ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት

እሑድ ጥቅምት 23 ቀን 1923 ዓ.ም በአዲስ አበባ ማሕል ከተማ በሚገኘው በቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን የተከናወነው የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የንግሥ በዓል፤ ከዚህ በፊት በኢትዮጵያ ነገሥታት ታሪክ ውስጥ ያልታየ ዝግጅት መሆኑ ይነገርለታል።

በበዓሉ ዋዜማ ጥቅምት 22 ቀን 1923 ዓ.ም ከምሽቱ አራት ሰዓት ጀምሮ፤ አዲሱ ንጉሠ ነገሥትና እቴጌይቱ በመሳፍንትና በመኳንንት ታጅበው በቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን በመገኘት፤ ሲጸልዩና ሲጸለይላቸው ካደሩ በኋላ፤ ከጠዋቱ አንድ ሰዓት እስከ አምስት ሰዓት ድረስ የንግሡ ሥርዓትና ጸሎተ ቅዳሴው ሲካሄድ ቆየ። በዚህ አራት ሰዓት ሙሉ ያለማቋረጥ በተከናወነው ፕሮግራም ላይ፤ ከልዩ ልዩ የውጭ አገር መንግሥታት መሪዎች ተልከው የመጡት ንጉሣውያን ቤተሰቦችና ከፍተኛ ባለሥልጣኖች፤ በየትኛውም ዓለም ከዚህ ቀደም ያላዩትን የንግሥ ሥነ ሥርዓት ለመከተል ምን ያህል ችግር እንደነበረባቸው እያንዳንዳቸው በየማስታወሻቸው ገልጸውታል ።

በቅዳሴው ላይ በየትኛው ፕሮግራም ከየወንበሮቻቸው ብድግ ብለው እንደሚቆሙ፣ ምን ሲባል ተመልሰው ወንበራቸውን እንደሚይዙ፣ ምን ጊዜ ደግሞ ወደ መሬት አቀርቅረው እንደሚጸልዩ፣ የሚያስረዳቸውና የሚመራቸው ባለመኖሩ፤ ብዙ መደናበር ደርሶባቸው እንደነበረ ሁሉም በየበኩላቸው ተርከውታል። በተለይ የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ መልዕክተኞች አምባሳደር ጃክቤና ጄኔራል ዊሊያም ሐርድ፤ ፕሮግራሙን መከተል ስለአቃታቸውና የክብር ባልደረባቸው የሆኑትም ራስ ጉግሣ አርዓያ ለመርዳት በመቸገራቸው፤ ቅዳሴውን አቋርጠው ሲወጡ ሊቀ ጳጳሱ አይተው በመቆጣት፤ የአሜሪካ መልዕክተኞች ወደ ክብር ቦታቸው ተመልሰው እንዳይገቡ ትዕዛዝ እስከ መስጠት ደርሰው ነበር። ኋላ ግን በብላቴን ጌታ ሕሩይ ወልደሥላሴ ብርታት፤ የአሜሪካ መልዕክተኞች ከቅዳሴው ፍጻሜ በኋላ፤ ለንግሡ ሥነ ሥርዓት ወደ ክብር ቦታቸው እንዲመለሱ ተደረገ። የሌሎቹ አገሮች የነገሥታትና የመንግሥታት እንደራሴዎች በተለይም የታላላቆቹ፤

- የእንግሊዙ ዱክ ኦፍ ግሉስተር፣
- የፈረንሣዩ ማርሻል ደስፔሬ፣
- የጣልያኑ ልዑል ፌርዲናንዶ፣ (የሳቮያ መስፍን)
- የጀርመኑ ባሮን ሉውዘን፣

የግብፃዊውን ሊቀጳጳስ የቅዳሴ አመራር በየአስተርጓሚዎቻቸው እየተረዱ፤ ሥነ ሥርዓቱን እስከመጨረሻው ለማስፈጸም ብዙ ጥረት አድረገዋል። በጠቅላላው ለውጭ አገር መንግሥታት መልዕክተኞች ብቻ ሳይሆን፤ ለኢትዮጵያውያኖቹም ቢሆን ለበዓሉ አከባበር ከፍተኛ አድናቆት የሰጠው፤ ከቅዳሴው ፍጻሜ በኋላ የተከናወነው አንድ ሰዓት ተኩል የፈጀው የንግሡ ሥነ ሥርዓት ነበር።

ንጉሠ ነገሥቱ የሚጭነውን ዘውድና የሚያጠልቀውን ልብሰ መንግሥት፤ በወገቡ የሚታጠቀውን ሰይፍና በእጁ የሚይዘውን በትረ መንግሥት፤ ከልዩ ልዩዎቹ የንግሥ ዕቃዎች ጋር፤ በጅሮንዱ (ማለት የገንዘብ ሚኒስትሩ) ከበዓሉ አንድ ሳምንት በፊት በክብር አጀብ ወስዶ ለቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን አለቃ

ካስረከበ በኋላ፤ ከየደብሩ የተመረጡት ዐርባ ዘጠኝ (49) ካህናት፤ ለሰባት ቀናት ሳያቋርጡ፤ በየቀኑ ዐርባ ዘጠኝ ጊዜ ዳዊት ሲደግሙበትና ሲጸልዩበት ሰነበቱ። ጥቅምት 23 ቀን 1923 ዓ.ም የንግሥ በዓሉ ሲጀምር፤ በቤተክርስቲያኑ መቅደስ ውስጥ የሐር ከፋይ ጨርቅ በለበሰ በአንድ ትልቅ ጠረጴዛ ላይ፤ አሸብርቀው የተደረደሩትን እነዚህን የንግሥ ዕቃዎች፤ ሊቀጳጳሱ አቡነ ቄርሎስ አንድ በአንድ ከባረኳቸው በኋላ፤ እያንዳንዳቸው በየተራ ለንጉሠ ነገሥቱ የቀረቡት በሚከተለው ሥነ ሥርዓት ነበር።

1. በወርቀዘቦ የተጠለፈውን ልብሰ መንግሥቱን አቡነ ይስሐቅ የሰሜን ኢትዮጵያ ጳጳስ ከላስታው መምህር ጋር ሆነው ንጉሠ ነገሥቱን አለበሱ።

2. በወርቅና በአልማዝ ያጌጠውን ትልቁን ሰይፍ፤ አቡነ ሳዊሮስ የደቡብ ኢትዮጵያ ጳጳስ፤ ከተድባበ ማርያም መምህር ጋር ሆነው ንጉሠ ነገሥቱን አስታጠቁ።

3. ከወርቅና ከአልማዝ የተሠራውን በትረ መንግሥት፤ አቡነ ሚካኤል የአዜብ ኢትዮጵያ ጳጳስ፤ ከሐይቁ መምህር ጋር ሆነው ንጉሠ ነገሥቱን በቀኝ እጃቸው አስያዙ።

4. ሕልቀተ ወርቁን ማለት፤ ከአልማዝ የተሠራውን የጣት ቀለበት አቡነ አብርሃም የምዕራብ ኢትዮጵያ ጳጳስ፤ ከመርጡለ ማርያም መምህር ጋር ሆነው በንጉሠ ነገሥቱ ቀኝ እጅ በአራተኛው ጣት ላይ አጠለቁ።

5. ሁለቱን ባለወርቅ ጦሮች፤ አቡነ ጴጥሮስ የምሥራቅ ኢትዮጵያ ጳጳስ ከደብረወገግ (አሰቦት) መምህር ጋር ሆነው ለንጉሠ ነገሥቱ አቀረቡ።

እነዚህ ከዚህ በላይ የተገለጹት የንግሥ ዕቃዎች ለነጋሚው ንጉሠ ነገሥት በወግ ከቀረቡ በኋላ፤ ቅብዓ መንግሥቱን መቀባትና ዘውዱን ባርኮ መጫን የግብፃዊው ሊቀ ጳጳስ የብፁዕ አቡነ ቄርሎስ ተግባር ሆነ። ቅብዓ መንግሥቱን ከደብረሊባኖስ በመጡት ፀባቴ፤ ዘውዱን ቈምስና ካላቸው ከአክሱም በመጡት መምህር አስይዘው፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ዙፋን እንደቀረቡ፤ አቡነ ቄርሎስ የሚከተለውን ጸሎት አደረጉ።

ቅዱስ አምላክ ሆይ፤ « .... ከተቀደሰው መንበረ መንግሥትህ፣ ከማይወሰነውም ሥልጣንህ፣ ከዘለዓለሙ ጌትነትህ፣ የሚያጽናናውን መንፈስ ቅዱስን (ጰራቅሊጦስን) በዚህ ቅብዓ መንግሥት ላይ ላክ ! የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በዚህ በተቀደሰው ቅብዓ መንግሥት ተቀብቶ የተከበረና የተቀደሰ እንዲሆን፤ የብርሃን መጐናጸፊያ ተጐናጽፎ፤ የሚቃወሙትን የመንግሥቱን ጠላቶች እንዲያሸንፍ፤ ከንዱን አበርታለት ! ..... አንተንም በምትወዳቸውና ደስ በሚያሰኙህ በቅዱሳን ነገሥታት መካከል እንደ ሰማይ ኮከብ ያበራ ዘንድ ጸጋህን ስጠው ! ቅዱስ አምላክ ሆይ፤ የብሉይ ነገሥታት ካህናትና ነቢያት፤ ሕዝብህን እስራኤልን እንዲገዙና እንዲያስተምሩ በተቀደሰ ቅባት እንደቀባሃቸው፤ አሁንም በዚሁ ልማድ አንተ የመረጥከውን አገልጋይህን ኃይለሥላሴን ባርከው ቀድሰው ! ..... ለኛም ለአገልጋይዎችህ በሰጠኸን ሥልጣን ቅብዓ መንግሥቱን ስንቀባው፤

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ይሆን ዘንድ ኃይልህን ስጠው ! በመንፈስህም አበርታው ! የጥበብና የማስተዋል፣ የዕውቀትና የምክር ኃይል አሳድርበት። ..... » ብለው ከጸለዩ በኋላ፤ ሊቀጳጳሱ ቅብዓ መንግሥቱን ይዘው እንደ ዳዊትና ሳዶቅ፣ ናታንና ሰሎሞን እኔም በዚህ በተቀደሰውና በተባረከው ቅብዓ መንግሥት እቀባዎታለሁ ብለው፤ ንጉሠ ነገሥቱን በመጀመሪያ ራሳቸውን፣ ቀጥሎ ደረታቸውንና ልባቸውን ቀቧቸው። የዚህ የቅብዓ መንግሥቱ አደራረግ እንደተፈጸመ፤ ሊቀጳጳሱ በንጉሠ ነገሥቱ ራስ ላይ ዘውዱን ከመጫናቸው በፊት፤ ጸሎታቸውን በመቀጠል፤ « ..... አቤቱ የታመንህ አምላካችን ሆይ ! ይህን ዘውድ ትባርከልን ዘንድ እንለምንሃለን። ይህንንም አገልጋይህን ንጉሣችንን ኃይለሥላሴን ከጥሩ ወርቅ የተሠራውን ይህን ዘውድ በራሱ ላይ እንደጫንክለት፤ የበጐነትንም ዘውድ በልቡ ጫንለት ! ..... » ብለው ዘውዱን ደፉላቸው።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ተብለው ቅብዓ መንግሥት የተቀቡትና የምኒልክን የዘውድ ሥልጣን የጫኑት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ በትረ መንግሥታቸውን በቀኝ እጃቸው ይዘው፤ በአልማዝና በወርቅ አጊጦ የተሠራውን ትልቁን ሰይፍ በወገባቸው በቀኝ በኩል እንዲያነግቡት በቀረበላቸው ጊዜ፤ የአቡነ ቄርሎስ ረዳት ሆነው የተመደቡት ጳጳስ የተናገሩት ቃል ሊጠቀስ የሚገባ ነው። « .... በዚህ ሰይፍ እውነተኛ ፍርድ ፍረድበት ! የእግዚአብሔርን ኦርቶዶክሳዊት ቤተክርስቲያን ጠብቅበት ! አገር ሲገነባ፤ የዋዘቀውን አቃናበት ! የታደሰውን አጽናበት ! በጐ ፈቃደኞችን ሹምበት ! ዐመፀኞችን ቅጣበት ! ..... » ሲሉ፤ ቀድሞ እጨጌ ሆነው የንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ የንስሐ አባት የነበሩትና አሁን ለደቡብ ኢትዮጵያ ጳጳስነትን የተሾሙት አቡነ ሳዊሮስ ከተናገሩ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ይህን ሰይፍ የታጠቁት፤ « .... አባቴ የተናገሩትን ሁሉ ለመፈጸም እንዲያበቃኝ፤ ፈጣሪዬን እለምነዋለሁ .... » የሚል ቃል አሰምተው ነው።

ከዚህ በኋላ የቀጠለው ፕሮግራም፤ የንጉሠ ነገሥቱ የሕይወት ጓደኛ ወይዘሮ መነን አስፋው፤ የእቴጌነቱን ዘውድ የጫኑበትና ልጃቸው መርዕድ አዝማች አስፋወሰን የአልጋወራሽነት የራስ ወርቅ አክሊል የተቀበሉበት ሥነ ሥርዓት ነበር።

በመጀመሪያ አልጋወራሹ ወደ ንጉሠ ነገሥቱ ዙፋን ቀርበው በጉልበታቸው ከተንበረከኩ በኋላ፤ ሊቀ ጳጳሱ ያቀረቡላቸውን የሚከተሉትን ጥያቄዎች እያዳመጡ መልሱን ሰጡ።

ሊቀጳጳስ፤ ለንጉሠ ነገሥትህና ለአባትህ በሕይወትህ ሁሉ ፍጹም አገልጋይ ለመሆን ትፈቅዳለህ ?

አልጋወራሽ፤ አክብር አባከ ወእመከ* የተባለውን ትዕዛዝ ሰምቻለሁና በፍጹም ልቤ እገዛለሁ።

* አባትና እናትህን



ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና እቴጌ መነን በንግሣቸው ዕለት፤
እ.ኢት.አቆ (ጥቅምት 23/1923 ዓ.ም

ሊቀጳጳስ፤ እንደ አቤሴሎም ደፍረህ፣ እንደ አዶንያስ ቸኩለህ፣ ከአባትህ ፈቃድ ለመውጣት፣ ያልተሰጠህን ለመሻት፤ ከሚመክሩህ ሁሉ ለመራቅ አጥብቀህ ትጠነቀቃለህ ?

አልጋወራሽ፤ ከአባቱ ፈቃድ የሚወጣ የተረገመ መሆኑን ስለማውቅ፤ ይህንን በመሰለው መንገድ አባቴን እንዳላስቀይም እጠነቀቃለሁ።

ሊቀጳጳስ፤ አባትህ ንጉሠ ነገሥት ፈቅደ፤ በምክር ቤት አስመክሮ ያቆመውን ሕግ፤ ከክፉ ሰዎች ጋር ተባብረህ እንቅፋት ሳትሆን፤ ሕጉን አክብሮ ለመጠበቅ ፈቃደኛ ትሆናለህ ?

አልጋወራሽ፤ ንጉሠ ነገሥቱ አባቴ ያቆመውን ሕግ እስከ መጨረሻው አክብሬ ለመጠበቅ እውነተኛ ፈቃዴ ነው።

አልጋወራሹ እነዚህን ከሊቀ ጳጳሱ የቀረቡላቸውን ጥያቄዎች ሁሉ መልስ ሰጥተው መሐላቸውን ከፈጸሙ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ « .... እግዚአብሔር የኃይሌና የሥልጣኔ፤ የዙፋኔና የዘውዴ ተቀባይ ያድርግህ ! .... » ብለው በትረ መንግሥታቸውን የያዙበትን ቀኝ እጃቸውን ዘረጉላቸው። በዚህ ጊዜ አልጋወራሹ « ... እግዚአብሔር እንደ ቃልዎ ያድርግልኝ ... » ብለው የአባታቸውን ቀኝ እጅ ከተሳለሙ በኋላ፤ ሊቀጳጳሱ የአልጋወራሽነት የዘውድ አክሊሉን ባርከውላቸው ወደ ተዘጋጀላቸው ልዩ ወንበር ሄደው ቦታቸውን ያዙ። የልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰን የአልጋወራሽነት ሹመትና የመሐላ ሥርዓት ከተፈጸመ በኋላ፤ የግርማዊት እቴጌ መነን የንግሥ በዓል ተጀመረ።

እቴጌይቱ በተለይ ለዚህ በዓል የተሰናዳላቸውን ልብሰ መንግሥታቸውን ለብሰው፤ በታወቁ ሴት ወይዛዝሮች ታጅበው፤ ከንጉሠ ነገሥቱ ቀኝ በተዘረጋላቸው የወርቅ ወንበር ላይ እንደተገኙ፤ የደቡብ ኢትዮጵያ ጳጳስ አቡነ ሳዊሮስ ለንግሥቲቱ የተዘጋጀውን ከአልማዝ የተሠራ ቀለበት ከዙፋኑ ጠረጴዛ ላይ አንሥተው፤ « .... የሃይማኖት ምልክት የሆነውን ይህን ቀለበት ይቀበሉኝ ! .... በዚህ ቀለበት ምልክትነት እግዚአብሔር ክብርዎን ከፍ ያድርገው። እሱንም ደስ የሚያሰኝ ሥራ ለመሥራት ያብቃዎ ! ..... » ብለው ከጸለዩ በኋላ፤ በንግሥቲቱ ቀኝ እጅ በአራተኛዋ ጣታቸው ላይ አጠለቁላቸው። ቀጥሎም፤ ከአክሱም ተመርጠው የመጡ ሁለት ቀሞሳት፤ የእቴጌይቱን ዘውድ ከመቅደሱ አውጥተው በዙፋኑ ፊት በተዘረጋው ጠረጴዛ ላይ ሲያስቀምጡ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ከወርቅ ወንበራቸው ላይ ብድግ ብለው፤ « .... እኔ ከእግዚአብሔር የተፈቀደልኝን ዘውድ ከእርስዎ እጅ እንደተቀበልኩት ሁሉ፤ የሕይወት ጓደኛዬ እቴጌ መነንም የሚገባትን ዘውድ ተቀብላ የክብሬ ተካፋይ እንድትሆን እውነተኛ ፈቃዴ ስለሆነ፤ ዘውዱን እርስዎ እንዲጭኑላት ብፁዕነትዎን እለምናለሁ። .... » ሲሉ፤ ሊቀጳጳሱን ጠየቁ። አቡነ ቄርሎስም « .... አቤቱ አምላካችን ሆይ ! በአገልጋይህ በወለተጊዮርጊስ* በእቴጌ መነን ላይ ይህን የክብርና የደስታ ዘውድ አኑርላት። የቸርነትና የርኅራኄ፣ የዕውቀትና የጥበብ ዘውድ አድርግላት .... » ብለው በመጸለይ፤ የወርቁን ዘውድ

* የወይዘሮ መነን የክርስትና ስም

ጫኑላቸው። ወዲያውም በበዓሉ ላይ ተካፋይ የሆኑት ሁሉ ከወንበራቸው ብድግ ብለው፣ ሴት ወይዛዝርቱ በዕልልታ፣ መሳፍንትና መኳንንት በጭብጨባ፣ ካህናቱና ዲያቆናቱ በከበሮና በጸናጽል ደስታቸውን ገለጹላቸው። በአዳራሹ ውስጥ ያስተጋባው የደስታ መግለጫ ረገብ ሲል፣ ሊቀጳጳሱ አቡነ ቄርሎስ ከወንበራቸው ብድግ ብለው፣ ከግብፅ አሌክሣንድርያ፣ ከመንበረ ማርቆስ የኦርቶዶክሳዊት ኢትዮጵያ የሃይማኖት አባት የሆኑት፣ ፓትርያርኩ ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ዮሐንስ ዐሥራ ዘጠነኛ፣ ለንጉሠ ነገሥቱ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያስተላለፉትን ከዚህ የሚከተለውን ልዩ መልዕክት አቀረቡ።

« .... ለእምቅድመ ዓለም በአምላክነቱ ብቻውን የሆነ፣ በአካል ሦስት የሆነ፣ የእውነተኛ አምላክ የአብ፣ የወልድ፣ የመንፈስ ቅዱስ በረከት፣ ለእግዚአብሔር ያደሩና የእግዚአብሔር ፍጹም ወዳጅ በሆኑት በንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ላይ ይደር እያልን እንጸልያለን።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፣ የኢትዮጵያን የንጉሠ ነገሥትነት ዘውድ በኢየሱስ ክርስቶስ ቸርነት የጫኑ፣ የእውነተኛይቱን ዕምነት የኦርቶዶክሳውያንን ቤተክርስቲያን ለመጠበቅ አደራ የተቀበሉ በመሆናቸው፣ የሰማይ መላዕክት ሁሉ ዙሪያቸውን ከበው እንዲጠብቋቸው፣ የመንፈስ ቅዱስ በረከት ሳይለያቸው፣ ደስ የሚያሰኘውን ረዥሙን የአገልግሎት ዘመንና የጤና ዕድሜ እንዲሰጣቸው፣ የቅድስት ንጽሕት እመቤታችን ድንግል ማርያምን፣ የእስክንድርያው ሐዋርያ የቅዱስ ማርቆስን፣ የሌሎቹንም የቅዱሳን ሰማዕታትን አማላጅነት እንለምናለን።

<u>ንጉሠ ነገሥት ሆይ፣</u>

የጌታችን የኢየሱስ ክርስቶስ፣ የአባታችን የእግዚአብሔር አብ ሰላም ከርስዎ ጋር ሆኖ፣ ከመንፈስ ቅዱስ ዕውቀትንና ጥበብን አግኝተው፣ ኢትዮጵያ ሥልጣኔዋ እየገፋ የሕዝቧ ሀብት እንዲለማ፣ መንፈሳዊ ዕምነቷ እየጠነከረ እንዲሄድና በዓለም ላይ የተከበረው ቦታዋ የላቀ እንዲሆን፣ የሚደክሙበት ሁሉ ፍሬ ሰጥቶ ለማየት እንዲያበቃዎ፣ ዘወትር በጸሎታችን ከርስዎ ጋር ነን። ይህችም የበረከት ቃል፣ ከመንፈሳዊው አባትዎ ከዮሐንስ ዐሥራ ዘጠነኛው፣ በጸጋ እግዚአብሔር የሐዋርያው ቅዱስ ማርቆስ መንበር፣ ከእስክንድርያው ፓፓና ፓትርያርክ ተጽፋ ቀርባልዎታለች። .... »

የኦርቶዶክሳዊት ኢትዮጵያ ቤተክርስቲያን አባት፣ የእስክንድርያው መንበረ ማርቆስ ፓትርያርክ የላኩት ይህ መንፈሳዊ መልዕክት በበዓሉ ላይ ከተገለጸ በኋላ፣ በሊቀጳጳሱ በአቡነ ቄርሎስ ገባሬ ሠናይነት ልዩ ቅዳሴ ተደርጐ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና ንግሥቲቱ እቴጌ መነን ሥጋ ወደሙ ተቀበሉ። በዚህ በቤተክርስቲያኑ ውስጥ የሚደረገው የንግሥ ሥነ ሥርዓት እንደተፈጸመ፣ ንጉሠ ነገሥቱና ንግሥቲቱ፣ በወርቅ ያንፀባረቀ ልብሰ መንግሥታቸውን ለብሰው፣ ዘውዳቸውን ጭነው፣ በትረመንግሥታቸውን ጨብጠው፣ ከቤተመቅደሱ ሲወጡ፣ ጳጳሳቱና ቀሳውስቱ የቅዱስ ጊዮርጊስን ታቦት ይዘው፣ መዘምራኑ " ብሩክ አንተ ንጉሠ እስራኤል " የሚለውን ወረብ እየወረቡ፣ በቤተክርስቲያኑ ዙሪያ ሦስት ጊዜ ዑደት ተደረገ። በዚህም ጊዜ፣ ራሶች መሳፍንትና መኳንንት የራስ ወርቅ አስረውና ባለወርቅ ለምድ ደርበው፣ ሊቀመኳሰች በከፋይ ቀሚስ ላይ በወርቅ የተንቆጠቆጠ ላንቃ ለብሰው፣ ሰይፈ ጃግሬዎች ባለወርቅ ጋሻና ጠበንጃ አንግበው፣ ከንጉሠ

ነገሥቱ በስተኂላ በዝግታ ሲራመዱ፣ ለአጀቡ ከፍ ያለ ድምቀት ሰጥተውት ነበር። በዚህ አኳኋን በቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን የተከናወነው የንግሥ በዓል በደህና ተፈጽሞ፣ ሊቀ ጳጳሱ አቡነ ቄርሎስ አሳርገው ታቦቱ ወደ ቤተመቅደሱ ከገባ በኂላ፣ ንጉሠ ነገሥቱና ንግሥቲቱ በወርቅ ሠረገላ ሆነው ወደ ቤተመንግሥታቸው ሲያመሩ፣ ከሕዝቡ የጕረፈላቸው የደስታ መግለጫ ከዚህ በፊት ታይቶ የማይታወቅ ነው እየተባለ ይነገራል።

ከቅዱስ ጊዮርጊስ ቤተክርስቲያን እስከ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ድረስ በተደረገው የአንድ ሰዓት የእርጋታ ጉዞ ላይ፣ እምቢልታውና መለከቱ ሲነፋ፣ ነጋሪቱ ሲጐሸም፣ ካህናቱ ሲዘምሩ፣ ወታደሩ ሲሸልል፣ ከዚህ ሁሉ ጋር የሴቱ ዕልልታና የወንዱ ጭብጨባ ሲያስተጋባ፣ የአዲስ አበባን የጥቅምት ፀሐይ እጅግ ያጋለው ይመስል ነበር። በዋዜማው ቅዳሜ፣ ከማታው በአራት ሰዓት የተጀመረው ጸሎተ ቅዳሴና የንግሥ በዓል ፕሮግራም የተፈጸመው፣ በማግሥቱ እሑድ ከቀኑ ስድስት ሰዓት ሲሆን፣ በዚህ ለዐሥራ አራት ሰዓቶች ያለማቋረጥ በተካሄደው ሥነ ሥርዓት ላይ፣ ንጉሠ ነገሥቱና ንግሥቲቱ ያሳዩትን ጥንካሬና የመንፈስ ጽናት ያላደነቀ አልነበረም። በተለይም በበዓሉ ተካፋይ ለመሆን ከአውሮፓ፣ ከእስያና ከአሜሪካ የመጡት የዐሥራ አንድ አገሮች እንደራሴዎች፣ ከዚህ ቀደም በየትኛውም ዓለም ያላዩትን ይህን እጅግ ረዥምና ከፍተኛ የሆነ ሥነ ሥርዓት ሲመለከቱ፣ ኢትዮጵያ ያላት ጥንታዊ ባህል ምን ያህል የሚደነቅና የሚከበር መሆኑን ለመገንዘብ የሚያስችላቸው ነበር። አብዛኛዎቹ መልዕክተኞች ለየመሪዎቻቸው በላኩት ራፖር፣ በንግሡ በዓል አከባበር መደሰታቸውን ቢገልጡም፣ መስተንግዶውን በሚመለከት ጉዳይ ያደረባቸውን ቅሬታ አልሸሸጉም። በመጀመሪያ፣ በታላላቆቹና በታናናሾቹ የመንግሥታት መልዕክተኞች መካከል የአቀባበልና የአስተነጋገድ ልዩነት መደረጉን አስተውለናል ብለዋል። ይኸውም፣ በንጉሠ ነገሥቱ ዙሪያ እጅግ የታወቁት ዋና ዋናዎቹ መስፍኖች፣

- ራስ ካሣ ኃይሉ ለእንግሊዝ መልዕክተኞች፣
- ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት ለጣልያን መልዕክተኞች፣
- ራስ ጉግሣ አርዓያ ለአሜሪካ መልዕክተኞች፣
- ራስ ሥዩም መንገሻ ለፈረንሣይ መልዕክተኞች፣

የክብር ባልደረቦች ሆነው በመመደባቸው፣ ለእነዚህ ለአራቱ መንግሥታት እንደራሴዎች ከሌሎቹ የበለጠ መንከባከብ እንደተደረገላቸው አድርገው ቆጥረውታል። ቀጥሎ ደግሞ እነዚሁ ታላላቅ የተባሉት አገሮች በአዲስ አበባ በባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር ደረጃ የሚመሩ ለጋሲዮኖች ስላሏቸው፣ የሚፈልጉትን ሁሉ እንደሚያገኙና ምንም ነገር እንዳልጐደለባቸው ተመልክተዋል። ሌሎቻቸው ግን፣ እንደ እነ ራስ ካሣ የመሳሰሉ ባልደረቦች ያልተሰጣቸው ከመሆኑም በላይ፣ ለጋሲዮን ስለሌላቸው፣ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት አዘጋጅቶ የጠበቃቸው የመኖሪያ ቤት የዘወትር የሕይወት ልማዳቸውን የሚያሟላላቸው አልሆነም።

እንደሚታወቀው፣ ለዚህ ንግሥ በዓል ዝግጅቱ የተጀመረው፣ ንግሥት ዘውዲቱ ከሞቱ በኂላ ስለሆነ፣ ከውጭ አገር መንግሥታት ተጋብዘው ለመጡት መልዕክተኞች በስድስት ወራት ጊዜ ውስጥ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው ተቆጣጥረው ያሠሩላቸው የማረፊያ ቤቶች፣ እጅግ አስፈላጊ የሆኑትን፣ እንደ ውሃ ማሞቂያና መታጠቢያ ቤቶች የመሳሰሉትን ሁሉ የሚያሟሉ ሆነው መገኘት አልቻሉም።



ልዑላን መሳፍንት፣ ከግራ ወደ ቀኝ ልዑል ራስ ሥዩም መንገሻ፣ ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣ ልዑል ራስ ኃይሉ ተ/ሐይማኖት፣ ልዑል ራስ ጉግሣ ዓርዓያ በንግሡ በዓል ዕለት፣

በእነዚህ ጉድለቶች እንግዶቹ ቅር መሰኘታቸው በግልጽ ታወቀ። "ሰው እንደቤቱ እንጂ፣ እንደ ጐረቤቱ አይኖርም" በሚለው አስተሳሰብ ዕምነት ያላቸው የቤተመንግሥቱ አስተናጋጆች፣ እንግዶቹ ያሳዩት የቅሬታ መንፈስ ትክክል ነው ብለው አልተቀበሉትም። « .... የመኝታ አልጋቸው በሐር አጉበር ተሸፍኖ፣ አዳራሻቸው ምን የመሰለ ሥጋጃ ለብሶ፣ መከዳቸው በሐር ጨርቅ አሸብርቆ፣ ቤቱ በሙሉ በኤሌክትሪክ ብርሃን አንፀባርቆ ሲጠብቃቸው፣ ከዚህ ሌላ ምን ኖርዋል ያስፈለጋቸው ? እንግዲህ ! እነሱ የሚጠይቁት እኛ የሌለንን ከሆነ፣ ምን ማድረግ እንችላለን ? ..... » በማለት የቤተመንግሥቱ ሰዎች እጅግ ተገርመው እንደነበረ ይነገራል። በተጨማሪም፣ ለእንግዶቹ የሚዘጋጅላቸው ምግብና መጠጥ፣ ከግብፅና ከጃፓን መልዕክተኞች በስተቀር፣ ሌሎቹ ለጤናችን ተስማሚ አይደለም በማለት አንመገብም ሲሉ፣ አሁንም ለአስተናጋጅነት የተመደቡት የቤተመንግሥቱ ኃላፊዎች እጅግ ተገረሙ። « .... ለፈረንጆች ጤንነት ተስማሚ ነው ብለን በልዩ ቦታ ተጠብቀው ከሚያድጉ ጥጆችና ወይፈኖች፣ በጉችና ፍየሎች እየመረጥን፣ በታወቁ ድርጆቶች የሚረቡ ዶሮዎችና ከእነሱ የተፈለፈሉ እንቁላሎች እየሰበሰብን፣ በሰጋ ቅቤና በአዋዜ ሠርተን ስናቀርብላቸው፣ እነዚህ ሁሉ ለጤናቸው የማይስማሙ ከሆኑ ምን ማድረግ እንችላለን ? .... ምናልባት እነሱ የሚፈልጉት በየአገራቸው እንደሚያደርጉት የዱር አራዊቱን እያደንን፣ አሳማውንና ሌላውንም እያግበሰበስን ምግብ አድርገን እንድንሠራላቸው ከሆነ፣ ልምዱም ሆነ ዕውቀቱ ስለሌለን እናዝናለን .... » ብለው እጃቸውን አጣምረው ተቀመጡ።

ይህ ችግር መድረሱን ንጉሠ ነገሥቱ እንደሰሙ፣ ወዲያውኑ በሰጡት ጥብቅ ትዕዛዝ መሠረት፣ በአዲስ አበባ ነዋሪ ለሆኑት የውጭ አገር ዜጐች በወጥ ቤትነት ከሚያገለግሉት ባለሞያዎች መካከል፣ ችሎታቸው የተደነቀላቸው እየተመረጡ በትውስት እንዲወሰዱና እንግዶቹ በሚፈልጉት ዓይነት ምግባቸው እየተሠራ እንዲቀርብላቸው ተደረገ። ይህ ከሆነ በኋላ፣ እንግዶቹም ወዲያውኑ ሐሳባቸውን ለወጡ። እንደዚያ ያን ሁሉ ወቀሳ ሲነዙ የነበሩትና በፍጥነት ወደ አገራችን መመለስ አለብን ብለው ሻንጣቸውን ማሰር የጀመሩት ሰዎች፣ የሚፈልጉትን በማግኘታቸው ተደስተው፣ አዲስ አበባንና አካባቢዋን በሚገባ ለመጐብኘት በተጨማሪ ጥቂት ቀናት መሰንበት አለብን አሉ። በሠለጠነው ዓለም አንድ እንግዳ ተጋብዞ ሲመጣ፣ ለእንግድነት የተወሰነለትን ጊዜ አስገዳጅ ሁኔታ ካልገጠመው በስተቀር፣ እንኳንስ ቀኑን ሰዓቱንም ቢሆን ለውጦ መቆየት አይችልም። ነገር ግን የኛ የኢትዮጵያውያኖች የአስተናጋጅ ልማድ ከሌላው ሁሉ ቸርነቱ የተለየ በመሆኑ፣ እነዚህ እንግዶች ለግብዣ ከተወሰነላቸው ጊዜ በላይ ለመቆየት ሲጠይቁ፣ በደስታ ከመፍቀድ በስተቀር፣ ምነው አልበዛም ወይ? አልተባሉም።

በአንድ ጊዜ የዐሥራ አንድ አገሮች መልዕክተኞች ጋብዞ ማስተናገድ በኢትዮጵያ ነገሥታት ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ ከልማድ እጥረትና ለመሰናዶውም በቂ ጊዜ ሳይኖር በመቅረቱ፣ የእንግዶቹ መቀበያ ዝግጅት በአንዳንዱ ረገድ ያልተሟላ ሆኖ ስለተገኘ፣ ይህን ያህል የሚያስቀጣ መሆን አልነበረበትም። ከዚህም በቀር የተዘጋጁላቸው የማረፊያ ሆቴሎች ምቹ ባለመሆናቸውና ብዙ ነገሮች የጐደሏቸው ሆነው በመገኘታቸው፣ አንዳንዶቹ መልዕክተኞች የኢትዮጵያን የወደፊት ዕድል በጨለማ መመልከታቸው እጅግ የሚያሳዝን ሆኗል።

በተለይም የጣልያኑ መልዕክተኛ ልዑል ፌርዲናንዶ ወደ አገሩ ሲመለስ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ለቤኒቶ ሙሶሊኒ ባቀረበው ራፖር፣ « .... እጅግ በሚያሳዝን ድህነት ሕዝቦቿ የሚሰቃዩባትና ወደፊትም ብቻዋን ከመከራው ዓለም ለመላቀቅ ተስፋ የሌላት ኢትዮጵያ፣ በምን ምክንያት የጀኔቩ የመንግሥታት ማህበር ተቀብሎ ከሠለጠኑት አገሮች እኩል የአባልነት ወንበር እንደሰጣት መመርመር ያስፈልጋል .... » እስከ ማለት ደርሷል። እንደተባለው፣ ይህ ጥያቄ ጀኔቭ ቢላክ መልሱን ለማግኘት ጊዜ እንደማይወስድ፣ የጣልያኑ መስፍን የተረዳው አይመስልም። ኢትዮጵያ የማህበሩ አባል የሆነችው፣ ከብዙ ሺህ ዓመታት ጀምሮ ነፃ መንግሥት ሆና የኖረችና ከዚህም በላይ ከጥንታዊው የተከበረ ታሪኳ ጋር የራሷ የሆነ ባህልና ሥልጣኔ ያላት አገር ስለሆነች፣ ከዓለም ማህበር ገበታ መለየት የለባትም ተብሎ በጣልያንና በሌሎቹ የአውሮፓ መንግሥታት የድጋፍ ድምፅ መወሰኑን ለመገንዘብ አስቸጋሪ አልነበረም። ነገር ግን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የንግሥ በዓላቸውን ባከበሩበት ዘመን፣ ሲኞር ሙሶሊኒ የኢትዮጵያን ነፃነት ለመግፈፍ የሚያልምበት ጊዜ መሆኑን፣ የፋሽስቱ መሪ ደጋፊዎች የሆኑት የጣልያን ንጉሣዊ ቤተሰቦች ምሥጢሩን ስለሚያውቁ፣ ልዑል ፌርዲናንዶ ከአዲስ አበባ ሲመለስ የሰጠው አስተያየት፣ ለዱቼ የቅርብና የሩቅ ዓላማ ደጋፊነቱን ለመግለጽ ሳይሆን አይቀርም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የሆኑበትን የንግሥ በዓላቸውን ሲያከብሩ፣ የደስታቸው ተካፋይ እንዲሆኑላቸው የጋበዟቸው የአውሮፓና የአሜሪካ ታላላቅ መንግሥታት እንደራሴዎች፣ በጉብኝታቸው ፍጻሜ ኢትዮጵያ በሥልጣኔ የገፋችና በሀብት የለማች አገር ነች ብለው አድናቆት እንዲሰጧቸው በመጠበቅ አይደለም። በዚያን ጊዜ የንጉሠ ነገሥቱ ዋና ዓላማ፣ እነዚህ የታላላቅ መንግሥታት መልዕክተኞች ከጉብኝታቸው ፍጻሜ በኋላ፣ ኢትዮጵያ ወደ ሥልጣኔ ለማምራት ያላትን ጽኑ ፍላጉትና የምታደርገውን ብርቱ ጥረት ተገንዝበው፣ ለእርምጃዋ የሚያስፈልጋትን እርዳታ ከየመንግሥታቸው ያስገኙላታል በሚል ተስፋ እንደነበረ፣ በዘመኑ የቅርብ አገልጋዮቻቸው ሆነው የሠሩት ሰዎች ሁሉ፣ ምስክርነታቸውን ሰጥተዋል።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፣ ለእነዚህ የዐሥራ አንድ መንግሥታት መልዕክተኞች፣ አንዳንድ ዋና ዋና ባልደረቦችና ረዳት አስተናጋጆች ተመድበውላቸው እንደነበረ ይታወሳል። ረዳት አስተናጋጆች ከተባሉት ውስጥ አብዛኛዎቹ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የክፍል ሹማምንቶች ስለሆኑ፣ እያንዳንዳቸው የእንግዶቹን አስተያየት እየቃረሙ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው የሚመለከቷቸው ራፖሮች እንዲያቀርቡ ልዩ ትዕዛዝ ስለተሰጣቸው፣ ሁሉም የተቻላቸውን ሠርተዋል። ከእነዚህም ሹማምንቶች መካከል አንዱ፣ ከሦስት ዓመት በፊት በዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል አስተርጓሚ የነበሩትና አሁን በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጣሊያንና የጀርመን ጉዳይ ኃላፊ የሆኑት አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ያቀረቡት ራፖር፣ የንጉሠ ነገሥቱን ልዩ አስተያየት የሚስብ ሆነ። ወልደጊዮርጊስ፣ ለተመደቡባቸው ለጣልያንና ለጀርመን እንግዶች ብቻ ሳይሆን፣ ወደ ሌሎቹም መልዕክተኞች ዘንድ ተሻግረው የሰበሰቧቸውን አስተያየቶች የገለጹት፣ በሚከተለው አኳኋን ነበር።

" ... በእኔ በትንሹ አገልጋይ አስተያየት፣ ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት ለጣልያኑ መልዕክተኛ ለልዑል ፌርዲናንዶ ዋና ባልደረባ ሆነው መመደባቸው

አይጠቅምም ብዬ ገና በዝግጅቱ ጊዜ ለበላይ አለቃዬ አመልክቼ እንደነበረ በታላቅ ትሕትና አስታውሳለሁ። በመጨረሻው፤ ውጤቱን እንዳየሁት፤ ይህ አቅርቤው የነበረው ሐሳብ የተሳሳተ አለመሆኑን አምኜበታለሁ። ይኸውም፤ የጣልያኑ መልዕክተኛ አዲስ አበባ ከደረሰበት ዕለት ጀምሮ፤ የበዓሉ ዝግጅት ብዙ ነገሮች የጐደሉትና ፕሮግራሙም እጅግ የተንዛዛ ነው በማለት፤ ብዙ ዓይነት ወቀሳ ከመግለጹም በላይ፤ ኢትዮጵያ በሥልጣኔ ወደ ኋላ የቀረችና የመሻሻል ዕድል የሌላት አገር ነች እያለ የሚናገረውን ዘለፋ፤ ራስ ኃይሉ እያዳመጡ ዝም ማለታቸውና ስድቡንም ያመኑበት መስለው መታየታቸው ነው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በንጉሠ ነገሥትነት በአደራ የተቀበሏት ኢትዮጵያ፤ በሥልጣኔ ወደ ኋላ መቅረቷንና ድህነቷን አልካዱትም። ደግሞም፤ ወደፊት በሥልጣኔ ገፍታ የበለጸገች አገር ለመሆን የቆረጠችና ብዙ ተስፋ ያላት አገር መሆኗን ከማስረዳት አልቦዘኑትም። እንደዚሁም፤ በጥንታዊው ታሪኳና በባህሏ፣ የራሷ በሆነው ሰብዓዊ ሥልጣኔዋና ሃይማኖቷ፣ ከማንም አገር ቀደምትነት ያላት መሆኗን በሙሉ ልብ ከመናገር ወደ ኋላ አላሉትም። ስለዚህ፤ የጣልያኑ መስፍን እናንተ ኢትዮጵያውያኖች ከሥልጣኔ እጅግ ወደ ኋላ የቀራችሁና ወደፊትም ለመሻሻል ተስፋ የሌላችሁ ናችሁ እያለ በንቀት ሲናገረን፤ አስፈላጊውን መልስ እንዲሰጡት አዘጋጅቼ ያቀረብኩላቸውን፤ ራስ ኃይሉ ሳይናገሩት በመቅረታቸው እጅግ የሚያሳዝን ሆኗል። ከዚህ በቀር ደግሞ፤ ራስ ኃይሉ ለጣልያኑ መልዕክተኛ የሰጡት አክብሮትና ያሳዩት ታዛዥነት፤ አገራችንን የሚያዋርድ መስሎ ስለታየኝ፤ በእኔ በትንሹ አገልጋይ ላይ፤ ያሳደረብኝን ከፍ ያለ ብስጭት ሳልገልጸው ማለፍ አልፈልግም።

አንድ፤ እንደ ኢትዮጵያ የመሰለ ነፃነቱን በሚያስደንቅ አኳኋን ተከላክሎ ያቆየ አገር፤ ከሠለጠነው ዓለም ተለይቶ ወደ ኋላ የቀረበት ምክንያት ምን እንደሆነ ሳይመረመር፤ ቀጥሎ ደግሞ ይኸው አገር፤ ወደ ሥልጣኔ ለማምራት ፍላጐት ያለው ወይም የሌለው መሆኑ ሳይታወቅ፤ በምን የተነሣ ተስፋ የለህም እየተባለ ይሰደባል ? .... በበኩሌ፤ የጣልያኑ መስፍን እንዲገነዘበው አዘጋጅቼ ለራስ ኃይሉ ያቀረብኩላቸው ሐሳብ ይህ ስለነበረ፤ ሳይፈጸም በመቅረቱ እጅግ አዝናለሁ። ይሁን እንጂ፤ ፕሮቶኮሉ ጥብቅ ሆኖ፤ እኔ በቀጥታ ከልዑል መስፍኑ ጋር ለመነጋገር ባይፈቀድልኝም፤ የክብር ተከታዮች ሆነው ለመጡት ለሴናተር ጋስፓሪኒ እና ለካቫሊየሬ ሚካኤል ስካማካ ሐሳቤን በሚገባ ገልጬላቸዋለሁ። « .... ተጋባዥ እንግዳ፤ ጋባዡን ለመዝለፍ ሲደፍር ታይቶ አይታወቅም .... »

ጉዳዩ በጠቅላላ ሲታይ፤ አብዛኞዎቹ መልዕክተኞች ምንም እንኳ ኢትዮጵያ እጅግ ወደ ኋላ ቀርታለች እያሉ የሚያስቡትን ባይሸሽጉንም፤ እንደ ጣልያኑ መስፍን ወደፊት ተስፋ የላችሁም በሚል አነጋገር ሞራላችንን ለመንካት አልሞከሩም። ይልቁንም፤ የጀርመን፣ የስዊድንና የሆላንድ መልዕክተኞች፤ አዲሱ ንጉሠ ነገሥት አገራቸውን ወደ ሥልጣኔ ለማሻገር ቁርጥ ሐሳብ እንዳላቸው የታወቀ ቢሆንም፤ ምን ያህል የተማሩ ወጣቶች ረዳት ለመሆን ይደርሱላቸው ይሆን? እያሉ የመጨነቅ ስሜት ከመስንዘራቸው በስተቀር፤ የኢትዮጵያን የወደፊት እርምጃ በጭለማ አይመለከቱም። ጓደኞቼና እኔም ለጠየቁን ሁሉ የሚያረካ መልስ የሰጠናቸው ይመስለኛል። ከመጡት እንግዶች መካከል ስለአገራችን ጉዳይ አንዳች አስተያየት ሳይሰጡ፤ የተደረገላቸውንም መስተንግዶ በአክብሮት እየተቀበሉ፤

አንድም ቀን ፈገግታ ሳይለያቸው፣ የተደሰቱ መስለው ወደየአገራቸው የተመለሱት የጃፓንና የግብፅ፣ የቱርክና የግሪክ መልዕክተኞች ናቸው።

እንግዲህ ! የዚህ ዓለም ታሪክ እንደሚነግረን ከሆነ፣ ሠልጥኖ የተወለደ አገር የለም። ሁሉም ዕድሉ ሲፈቅድለት፣ መከራንና ፈተናን ለብዙ ዘመናት እየተቀበለ፣ ከሥልጣኔ ደረጃ ለመድረስ የበቃ ነው። የእኛም ኢትዮጵያ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን የመሰለ መሪ ለማግኘት በመታደሏ፣ ፈተናዎቿን ሁሉ ጠንክራ ለማለፍና አንድ ቀን የሥልጣኔ ብርሃን ተጐናጽፋ ለመታየት እንደምትበቃ መታመን አለበት። ጓደኞቼና እኔ ዕድል ባጋጠመን ቁጥር፣ ፈረንሣዊኛ ለሚናገሩት እንግዶች ሁሉ ለማስረዳት የሞከርነው በዚህ መንፈስ ነው። እንግዶቻችን በሙሉ አገራችን በሰነበቱበት ጊዜ፣ አንዳች እክል ሳይገጥማቸው ባለው አቅም ሁሉ ተስተናግደው፣ ወደየአገራቸው በደህና በመመለሳቸው፣ ንጉሠ ነገሥታችንና መንግሥታቸው የሰላም ዕረፍት ማድረግ ይገባቸዋል ... "

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለንግሥ በዓላቸው የጋበዟቸው እንግዶች፣ አስተያየታቸው ምን እንደሆነ፣ ከልዩ ልዩ ወጣት ዲፕሎማቶች ከደረሳቸው መረጃዎች ውስጥ፣ ከዚህ በላይ እንደታየው ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ባቀረቡት ሪፖርት፣ እውነተኛውን ሁኔታ ገልጸው በመናገራቸው እጅግ ሲደሰቱ፣ በሌላ በኩል ደግሞ፣ ኢትዮጵያን ወደ ሥልጣኔ ለማሸጋገር ያላቸውን ጽኑ ፍላጐት፣ የየመንግሥታቱ እንደራሴዎች ግምት ያልሰጡት መሆናቸውን በመስማታቸው እጅግ አዝነዋል። ኢትዮጵያን ለማሻሻል ለሚደረገው ጥረት ምን ዓይነት እርዳታ እንደሚያስፈልግ በመነጋገር ፋንታ፣ አገሪቱ ዛሬ የምትገኝበትን የድህነት ሕይወት እያወገዙ መንቀፍና ለወደፊቱም ተስፋ የሌላት አገር ነች የሚል አስተያየት መስጠት፣ የንጉሠ ነገሥቱን ሞራል የሚነካ እንጂ፣ የሚያበረታታ አልሆነም። አዲሱ ንጉሠ ነገሥት፣ በ1916 ዓ.ም አልጋወራሽ በነበሩበት ዘመን አውሮፓን ጐብኝተው ከተመለሱ በኋላ፣ ኢትዮጵያ ካልሠለጠነች ነፃነቷ እንደሚገፈፍና ለመሠልጠንም ዕድል የምታገኘው፣ በሥልጣኔ ከገፉት አገሮች ጋር በወዳጅነት ስትተሳሰር ነው ብለው ያቀረቡትን ሐሳብ፣ አባ መቻል ሀብተጊዮርጊስና ሌሎቹም ዋና ዋናዎቹ ሚኒስትሮች እንዳልተቀበሏቸው ይታወሳል። በዚያን ጊዜ የምኒልክ መኳንንቶች የነበራቸው አስተያየት፣ « .... ኢትዮጵያ ከፈረንጆች ጋር የተሳሰረ ወዳጅነት ይጐዳታል እንጂ አይጠቅማትም። ወዳጆች ነን እያሉ የሚቀርቡን፣ የጉልበታችን ኃይል እስከምን ድረስ መሆኑን ለመገመት ስለሆነ፣ ገና ለገና ያሠለጥኑናል ብለን ነፃነታችንን እንዳናጣ መጠንቀቅ አለብን .... » የሚል ነበር። የምኒልክ ምርቶች የሆኑት ታላላቅ ሰዎች ይህን የመሳሰለውን አቋም በመውሰዳቸው፣ ተራማጅ የሆኑት አልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን፣ ለኢትዮጵያ መሻሻል እንዳይሠሩ እንቅፋት ሆኑባቸው እየተባሉ ምን ያህል ይወቀሱ እንደነበረ ይታወሳል። አሁን ደግሞ እነዚህ " አስቸጋሪ " የተባሉት ሰዎች፣ ይህን ዓለም ለቅቀው ከሄዱ በኋላ፣ ለአዲሱ ንጉሠ ነገሥት ሜዳው ነፃ በሆነላቸው ጊዜ፣ ኢትዮጵያን ለማሠልጠን ይረዱኛል ብለው ተስፋ የጣሉባቸው የአውሮፓ መንግሥታት፣ እንኳንስ የጠበቁትን ሁሉ ሊለግሷቸው ይቅርና በራሳቸው አቅም ለሚያደርጉት ጥረት እንኳ የሞራል ድጋፍ ሳይሰጧቸው ቀሩ።

ተፈሪ መኰንን ገና ከልጅነታቸው ዘመን ጀምሮ የሚደነቁበት ትልቁ ችሎታቸው፣ ከብልህነት ጋር የተጣመረው ትዕግሥታቸውና በቀላሉ ተስፋ የማይቆርጠው የመንፈስ ጥንካሬያቸው ነው። ስለዚህም፣ ለንግሥ በዓላቸው

የመጡት የአውሮፓ መንግሥታት እንደራሴዎች፤ በአገሪቱ ጊኋ ቀርነትና በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ፊዎዳላዊ አስተዳደር ነቀፌታቸውንና ወቀሳቸውን ከማዝነብ በስተቀር፤ ለኢትዮጵያ ልማት የሚረዳ አንዳች ሐሳብ ሳይሰነዝሩ መመለሳቸው ቢያሳዝናቸውም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ተስፋቸውን አልቆረጡም። እነዚህ በሥልጣኔ የገፉት አገሮች የኢትዮጵያን መሠረታዊ ችግር ዛሬ ለመገንዘብ ባይችሉም፤ ነገ ዓይናቸውን ከፍተው በሚገባ የሚያዩበት ጊዜ ይመጣል በሚል ዕምነት፤ ያለፈውን ማሕደር ዘግተው የወደፊቱን በተስፋ ማዘጋጀት ቀጠሉ።

በአገራችን አነጋገር፤ ነገሥታቱ ሲነግሡ ሕዝብ አንጋሽ፤ ቤተክርስቲያን ቀዳሽ፤ እንደተባለው ተፈሪ መኰንን በክርስትና ስማቸው ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ተብለው ዘውድ በጫኑበት ዕለት፤ የቤተክርስቲያናችን መሪ ሊቀ ጳጳሱ አቡነ ቄርሎስ በሰጡት ቃለ ቡራኬ፤ « .... በርስዎ መሪነት ኢትዮጵያ ዘመናችን ያፈለቀውን ሥልጣኔ አግኝታ በዓለም ላይ የክብር ቦታ እንድትይዝ፤ የሚያደርጉት ጥረት የተባረከ ይሁን .... » ብለው መርቀዋቸዋል። አፄ ምኒልክ፤ ጥቅምት 24 ቀን 1882 ዓ.ም የመላዋ ኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ሆነው ዘውዳቸውን በጫኑበት ዕለት፤ የቤተክርስቲያናችን መሪ አቡነ ማቴዎስ የሰጧቸው ቡራኬ፤ « ኢትዮጵያን ለማስፋፋትና አንድነቷን ለማስተሳሰር ቸሩ ፈጣሪያችን ድካምዎን ይባርክልዎ » የሚል ነበር። ይህ ከተባለ ከዐርባ ዓመታት በኋላ፤ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተሰጠው ቡራኬ፤ አፄ ምኒልክ ያስፋፏትን ትልቋን ኢትዮጵያ ለማሠልጠንና ለማልማት ስለሆነ፤ ከዚህ ጊዜ ጀምሮ በተፈጸመው በዐርባ አራት ዓመታት የመሪነት ዘመናቸው ውስጥ፤ የቤተክርስቲያናችንን መሪዎች ምርቃትና የሕዝባችንን ምኞት ከግብ ለማድረስ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ያደረጉት ጥረትና የታየው ውጤት ምን እንደሆነ፤ ይህ የታሪክ መጽሐፍ አብራርቶ ለማቅረብ ይሞክራል።

<u>መረጃ፤</u> ስለ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንግሥ በዓል አከባበርና ስለ ፕሮቶኮሉ ሥነ ሥርዓት፤ ከቤተመንግሥቱ የተዘጋጀው ፕሮግራም የበዓሉን አፈጻጸም በዝርዝር ያስረዳል።



ግርማዊት እቴጌ መነን አስፋው፤

**"ከአንድ አካልና ከአንድ አምሳል ልዩነት ስለሌለው፤ ይኸው በእቴጌይትነቱ ስም እንድትጠሪ ፈቅደንልሻል"**

*ቀ.ኃ.ሥ* (ጥቅምት 23/1923 ዓ.ም)

# ምዕራፍ ፪

## ከፍጹም ፊውዳላዊ ሥርዓት ወደ ሕጋዊ አስተዳደር

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ ከምኒልክ ሲያያዝ የመጣውን ዘውድ በጫኑ በዘጠነኛው ወር፤ ሐምሌ 9 ቀን 1923 ዓ.ም፤ ኢትዮጵያ በሕገ መንግሥት የምትተዳደር የንጉሠ ነገሥት አገር መሆኗን ለሕዝባቸውና ለሌላውም ዓለም ሕዝብ በአዋጅ አስታወቁ።

በኢትዮጵያ ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ የቆመው ይህ ሕገ መንግሥት፤ ለሕዝቡ ምን ጥቅም ይሰጣል ተብሎ እንደታሰበና፤ ዝግጅቱም በምን አኳኋን እንደተከናወነ ከመግለጻችን በፊት፤ አዲሱ ንጉሠ ነገሥት ይህን እርምጃ የወሰዱት በምን ምክንያት እንደሆነ ለማወቅ መሞከር አስፈላጊ ይሆናል። ወደ ኋላ መለስ ብለን የሩቁን ሳይሆን የቅርቡን ዘመን ታሪክ ብቻ ብንመለከት፤ ከቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በፊት የነበሩት ነገሥታት ሁሉ አገራቸውንና ሕዝባቸውን የመሩት፤ ከጥንት ሲያያዝ የመጣውን መሠረታዊውን የኢትዮጵያን ልማድ በመከተል ነው እንጂ፤ በሕግ የቆመ የአስተዳደር ደንብ አልነበራቸውም። በተለይም በዓለም ላይ የሥልጣኔ ብርሃን በፈነጠቀበት ዘመን፤ በቅደም ተከተል ኢትዮጵያን በአንድነት የመሯት ነገሥታት፤ አፄ ቴዎድሮስ ሆኑ አፄ ተክለጊዮርጊስ፣ አፄ ዮሐንስ ሆኑ አፄ ምኒልክ፣ ሕዝባቸውን የሚያስተዳድሩበት ሕገ መንግሥት አልመሠረቱም። ሆኖም፤ አባ ዳኘው ምኒልክ በ1900 ዓ.ም ያቋቋሟቸው ልዩ ልዩ የሚኒስቴር መሥሪያ ቤቶችና የሚኒስትሮች ምክር ቤት የተግባር ምዕዳን፤ ሕዝባቸውን የሠለጠነው ዓለም በሚከተለው መንገድ ለማስተዳደር የነበራቸውን በጎ ፈቃድ በትክክል ያመለክታል።

ከምኒልክ ዘመነ መንግሥት ፍጻሜ በኋላ፤ በወግ ዘውድ ጭነው ሳይነግሡ ለአምስት ዓመት ከአምስት ወር በሙሉ ሥልጣን የኢትዮጵያ መሪ የነበሩት አቤቶ ኢያሱም፤ አገሪቱን በሕግ ለማስተዳደር ፍላጐት አላሳዩም። የሸዋ መኳንንት መክሮ ልጅ ኢያሱን ከሥልጣን በማውረድ የኢትዮጵያ ንግሥተ ነገሥታት አድርጎ ያነገሧቸው ዘውዲቱ ምኒልክም፤ ለኢትዮጵያ ሕዝብ መተዳደሪያ ሕገ መንግሥት ያስፈልጋል የሚል ሐሳብ አልነበራቸውም።

እንግዲህ ! ከአባ ዳኘው ምኒልክ ቀጥሎ በሦስተኛ ደረጃ የኢትዮጵያን መሪነት የተቀበሉት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ፤ በነገሡ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ በማን አስገዳጅነት ወይም በማን ጠያቂነት ሕገ መንግሥት ለማቆም እርምጃ ወሰዱ? የሚል ጥያቄ ለሚያቀርቡት ሰዎች፤ ትክክለኛውን መልስ ማግኘት ያስፈልጋል።

ሐምሌ 9 ቀን 1923 ዓ.ም ዘውድ በጫኑ በዘጠነኛው ወር፤ ይህን ለኢትዮጵያ መጀመሪያ የሆነውን ሕገ መንግሥት አዘጋጅተው ሲያቀርቡና፤ ቀጥሎም ከአራት ወር በኋላ ጥቅምት 23 ቀን 1924 ዓ.ም የመጀመሪያውን

ፓርላማ ሲከፍቱ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሰጡትን መግለጫ መሠረት አድርገን ጉዳዩን ካጠናነው፤

በእርግጥ ! ሕገ መንግሥት እንዲሰጡ ከሕዝቡ አንዳች ጥያቄ እንዳልቀረበላቸው፤

በእርግጥ ! የተቀዋሚዎች ወገን ከሆኑት ወይም ከወታደሩ ክፍል፤ አገሪቱን በሕገ መንግሥት እንዲያስተዳድሩ ምንም ዓይነት ተጽዕኖ እንዳልተደረገባቸው የታወቀ ስለሆነ፤ " ሕዝባችንን ወደ ሥልጣኔ ለመምራት ማንም ሳይጠይቀን እኛው ራሳችን ወደንና ፈቅደን ይህን ሕገ መንግሥት አቁመናል " ብለው የተናገሩት ቃል፤ ትክክለኛ መሆኑን መቀበል ያስፈልጋል።

ይሁን እንጂ፤ የተሰጠው ሕገ መንግሥት በበጎ ፈቃድ መሆኑ ባያጠራጥርም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በነገሡ ማግሥት፤ የመሳፍንቱንና የመኳንንቱን ሙሉ ድጋፍ ሳያገኙ ይህን ውሳኔ ለማድረግ ለምን እንደፈጠኑ በአገር ውስጥ ልዩ ልዩ የሆነ ትርጉም ሲሰጠው እንደቆየ ይታወሳል። በዚህ ጉዳይ አንዳንድ የውጭ አገር ጋዜጠኞች ባደረጉት ምርምር፤ .... እንደ ጣልያን የመሳሰሉት የአውሮፓ ኮሎኒያሊስቶች ኢትዮጵያን ከጭለማው ዓለም ውስጥ አውጥተን የሥልጣኔውን መንገድ እንድትከተል ማድረግ አለብን በሚል ሰበብ፤ አንድ ቀን ነፃነቷን ከመግፈፍ እንደማይመለሱ ተፈሪ መኰንን ስለተረዱት፤ አንዳንድ የመሻሻል እርምጃዎች እየወሰዱኩ፤ ጠላቶቼን ሳይቀድሙኝ ልቅደማቸው ብለው ነው ሲሉ አስተያየታቸውን ሰጥተዋል። የዚህ መጽሐፍ ደራሲም የዚህን አስተያየት ትክክለኛነት ይቀበላል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በአልጋወራሽነታቸው ዘመን በ1916 ዓ.ም አውሮፓን በጎበኙ ጊዜ፤ ታላላቆቹ መንግሥታት ስለ ኢትዮጵያ ያላቸውን ግምትና አስተያየት አተኩረው ሲመለከቱ፤ አገሪቱ ከፊውዳል አስተዳደር ለመላቀቅ፤ አንዳንድ የመሻሻል እርምጃ ሳታደርግ፤ ባለችበት ሁኔታ የቀጠለች እንደሆነ፤ ነፃነቷን ይዛ ለመቆየት ዋስትና እንደሌላት ተገንዝበዋል። ይህንንም የሥልጣኔ ጉዳና ለመከተል፤ ከኮሎኒያሊስቶቹ መንግሥታት አንዳንድ መሠረታዊ የሆነ እርዳታ ለማግኘት እንደጠየቁና፤ አዲስ አበባም ከተመለሱ በኋላ፤ የአገሩን የውስጥ አስተዳደር ለማሻሻል፤ ከንግሥቲቱ ጀምሮ የመሳፍንቱንና የመኳንንቱን ድጋፍ ለማግኘት ምን ያህል እንደጣሩ፤ ከዚህ በፊት በታተመው "ተፈሪ መኰንን" በተባለው መጽሐፍ በሰፊው የተገለጸውን መመልከት ያስፈልጋል።

የአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን ታሪክ በግልጽ እንዳሳየው፤ ኮሎኒያሊስቶቹ ጦራቸውን እያዘጋጁ፤ በአፍሪካም ሆነ በእስያ የሚገኙትን አገሮች፤ ቅኝ አድርገው ለመግዛት የሚያግዳቸው ነገር አልነበረም። በሐያኛው ክፍለ ዘመን ግን፤ በተለይ እንደ ኢትዮጵያ የመሰለውን ነፃነቱ በዓለም ላይ የታወቀለትን አገር፤ ቅኝ ግዛት ለማድረግ ቀላል ነገር ስላልሆነ፤ ወራሪው ኮሎኒያሊስት ከሁሉ አስቀድሞ ከጓደኞቹ ጋር ተነጋግሮ መስማማትና የሆነ ያልሆነ ምክንያት እየደረደረ የዓለምን ሕዝብ አስተያየት ለማወናበድ፤ ከፍተኛ የሆነ የፕሮፓጋንዳ ቅድመ ዝግጅት ያስፈልገው ነበር። ለምሳሌ፤ በአሥራ ዘጠነኛው ክፍለ ዘመን ማክተሚያ ላይ ኮሎኒያሊስቱ ጣልያን ኢትዮጵያን ለመያዝ ጦሩን አሰናድቶ በአድዋ በኩል የመጣው፤ አፄ

ምኒልክ ውጫሌ ላይ በሁለቱ አገሮች መካከል የተፈረመውን ውል አለአግባብ አፈረሱብኝ በሚል የተጭበረበረ ሰበብ እንደነበረ ይታወሳል። አሁንም በዚህ በሐያኛው ክፍለ ዘመን ምንጊዜም የማይተኛልን ጠላታችን ጣልያን፤ ከሌሎቹ ጓደኞቹ ኮሎኒያሊስቶች ጋር ተስማምቶ፤ አንድ ምክንያት በመፍጠር ነፃነታችንን ለመድፈር ይሞክር ይሆናል በማለት፤ ተፈሪ መኰንን ጥርጣሬና ሥጋት እንደነበራቸው ታውቋል። ስለዚህም፤ ለኢትዮጵያ ነፃነት ትልቅ ዋስትና ሰጭ ነው ብለው የሚተማመኑበት የመንግሥታት ማሕበር፤ ለአገራቸው ዘመናዊ አስተዳደር እንዲመሠርቱና የሕዝቡንም ሰብዓዊ መብት ለመጠበቅ የተፋጠነ እርምጃ እንዲወስዱ፤ አጥብቆ የጠየቃቸውን ሁሉ ለመፈጸም፤ የተቻላቸውን ሁሉ ለማድረግ ሞክረው ነበር። ከእነዚህም መሻሻል አለባቸው ከተባሉት ዋና ዋና ጉዳዮች መካከል፤

1ኛ/ የሰው ልጅ "ባሪያ " እየተባለ የሚፈጸመው የግፍ ንግድ እንዲቀር፤

2ኛ/ ነፍስ ገድለሀል ተብሎ የሙት በቃ በተፈረደበት ሰው ላይ የሚፈጸመው፤ እጅግ አሰቃቂ የነበረው ቅጣት እንዲሠረዝ፤

3ኛ/ ዘመናዊ ትምህርት ቤቶች ተከፍተው የኢትዮጵያ ልጆች በብዛት እንዲማሩ አስፈላጊዎቹ ሕጐች በአዋጅ ወጥተው በተግባር እንዲውሉ ማድረግ ነበር።

ይሁን እንጂ ኢትዮጵያ የመንግሥታት ማህበር አባል ከሆነች በኋላ፤ በስድስት ዓመት ጊዜ ውስጥ፤ ተፈሪ መኰንን እነዚህን የሰውን ልጅ መብት የሚመለከቱትን ዋና ዋና ጉዳዮች ለማሻሻል ብዙ ችግርና ፈተና ቢያሳልፉም፤ ገኔቭ በሚገኙት በድርጅቱ ባለሥልጣኖች ዘንድ፤ የተሠሩት ሥራዎች ሁሉ የሚመስገኑ ናቸው ተብሎ የሚያበረታታ አስተያየት አልተሰጣቸውም። ይልቁንም ከጥንት ጀምሮ ሲሠራበት የቆየውን የባሪያን ንግድ ለማጥፋት መንግሥት አዋጅ በማውጣትና በወንጀለኛው ላይ ቅጣቱን ከፍ በማድረግ ብቻ ሳይወሰን፤ በመላው የኢትዮጵያ ግዛት ሕገ ወጦችን (ማለት ባሪያ ነጋዴዎችን) እያደነ የሚይዝና ለፍርድ የሚያቀርብ ድርጅት ማቋቋም፤ እጅግ አስፈላጊ መሆኑን ተጨማሪ ማሳሰቢያ እስከ መላክ ደረሰ።

ተፈሪ መኰንን በዚያን ጊዜ ያላቸው የቀደመ አስተያየት፤ አገራችንን ከፊውዳል የአገዛዝ ሥርዓት ወደ ዘመናዊ አስተዳደር ለመለወጥ፤ አፄ ምኒልክ የጀመሩትን የባሪያን ነፃነት አዋጅ በማጠንከር ብቻ የተወሰነ አልነበረም። ከዚህም ጋር መሻሻል ያለባቸው ጉዳዮች ብዙዎች ስለሆኑ፤ ከአውሮፓ ጉብኝታቸው መልስ በንግሥቲቱ ዙፋን ዙሪያ በተደረገው የመሳፍንትና የመኳንንት ታላቅ ስብሰባ ላይ፤ መንግሥት ምን እርምጃ መውሰድ እንዳለበት፤ (በተለይ ስለ ዘመናዊ ትምህርት ማስፋፊያ) ያቀረቡትን ሐሳብ፤ እንኳንስ የሚደግፋቸው በጥሞና የሚያዳምጣቸው እንኳ ሳያገኙ ቀሩ። ቢቸግራቸው፤ ከምሬታቸው የተነሣ፤ « .... ኢትዮጵያ እኮ መሠልጠን እንዳለባት ለዓለም ተጋልጣለች። ወደፊት እንጂ ወደ ኋላ ማለት አትችልም። .... » የሚል ጩኸት ባሰሙ ጊዜ፤ « .... ኢትዮጵያን ያጋለጣት ማን ነው ? ብሎ መጠየቅ ይቻል የለም ወይ ? .... » ሲሉ፤ አባ መቻል ሀብተጊዮርጊስ የተከሱባቸው መድፍ፤ የአልጋወራሹን የተራማጅ መንፈስ ምን ያህል እንደገታው መመዘን አያስቸግርም። በዚህም አኳኋን፤ የኢትዮጵያን አስተዳደር ለማሻሻል ለገኔቡ የመንግሥታት ማህበር የሰጡትን ቃል እንደተመኙት ሁሉ ለመፈጸም የማይቻል ሆነባቸው። ስለዚህ፤ የነ አባ መቻልና የነ ዘውዲቱ ዘመን እስከሚያበቃ

ድረስ፣ ለተወሰኑ ዓመታት በትዕግሥት ከጠበቁ በኋላ፣ ንጉሠ ነገሥት ሆነው ሙሉ ሥልጣን በጨበጡ ማግሥት፣ « .... ኢትዮጵያ በሕገ መንግሥት የምትተዳደር ንጉሣዊ አገር ነች .... » ተብላ በዓለም ላይ እንድትታወቅ ለማድረግ፣ አስቸጋሪውን እርምጃ ወሰዱ።

## ምን ዓይነት ሕገ መንግሥት ?

ከሁሉ አስቀድሞ ንጉሠ ነገሥቱ ለኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ማቆም በምን ምክንያት እንዳስፈለጋቸው፣ ቀጥሎም ለአገሩም ሆነ ለሕዝቡ የሚሰጠው ጥቅም ምን እንደሆነ፣ ለመሳፍንትና ለመኳንንት አስረድቶ ለማሳመን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የገጠማቸው ችግር ቀላል አለመሆኑን ማየት ያስፈልጋል።

ንጉሠ ነገሥቱ የንግሥ በዓላቸውን ባከበሩ ማግሥት፣ በቤተመንግሥታቸው መሳፍንቱንና መኳንንቱን፣ ሚኒስትሮቹንና የጦር አለቆቹን፣ ጳጳሳቱንና የቤተክህነት መሪዎቹን ሰብስበው፣ ለኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ማዘጋጀትና በአስቸኳይ ሥራ ላይ እንዲውል ማድረግ እጅግ አስፈላጊ መሆኑን ለማስገንዘብ የሰጡት መግለጫ የሚከተለው ነበር።

« .... ሁላችሁም እንደምታውቁት ከቀዳማዊ ምኒልክ ጀምሮ ለብዙ ሺህ ዓመታት እስከአሁን የቆየው የኢትዮጵያ አገዛዝ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ብቻ በሥልጣኑ እያዘዘ እንደአሰኘው የሚሠራ እንጂ፣ ምክር ቤት አቋቁሞ በሕገ መንግሥት ያስተዳደረ ንጉሥ የለም። በአውሮፓና በእስያም አገሮች በቀድሞው ዘመን ነገሥታቱ ሕዝቡን የሚገዙት ያለ ሕገ መንግሥት ስለነበረ፣ በሕዝቡና በአስተዳዳሪዎቹ መካከል በተፈጠረው ሁከት ምክንያት ምን ያህል መከራና ስቃይ እንደደረሰ፣ ያለፉት ታሪኮች ይነግሩናል። በአገራችን በኢትዮጵያም፣ ይኸ እንዳይደርስ ለአገዛዛችን ሕግ እንዲኖረው፣ ሕዝባችንም ደረጃ በደረጃ ለመንግሥቱ ሥራ ተካፋይና ረዳት እንዲሆን ለማድረግ፣ ለወራሾቻችንም በሕግ የተመሠረተ አስተዳደር ለማቆየት፣ ሕገ መንግሥት ተዘጋጅቶ እንዲቆም መድከም የጀመርነው ገና አልጋወራሽና ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ሆነን በምንሠራበት ጊዜ ነበር። ነገር ግን በዚያን ጊዜ ያለ ሕግ አገርን መግዛት ጥቅማቸው የሆነ ታላላቅ ሰዎች፣ የሕገ መንግሥት መቆም የንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱን ማዕረግና ሥልጣን የሚቀንስ እያስመሰሉ በመናገር ስለተቃወሙን፣ ሐሳባችንን ለመፈጸም ሳንችል ቆየን።

አሁን ግን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ሆነን ዘውዱንና ዙፋኑን በሕግ ስለወረስን፣ ከብዙ ጊዜ ጀምሮ አስፈላጊነቱን አምነን ስናስብበት የነበረውን ሕገ መንግሥት ለማቆም ቆርጠን ተነሥተናል። ሁላችሁም እንደምታውቁት ኢትዮጵያ ዤኔቭ ላይ በተቋቋመው የዓለም የመንግሥታት ማህበር አባል ሆና በሥልጣኔ እጅግ ከተራመዱት አገሮች ጋር ለክፉም ሆነ ለደጉ አብሮ የመሥራት ዕድል አጋጥሟታል። የማህበሩም ዋና ዓላማ በመንግሥታት መካከል ፍቅርንና ሕብረትን የሚገነባ፣ ኃይለኛው ደካማውን እንዳያጠቃ የሚከላከል፣ ነፃነትንና ሰላምን ለማጠንከር የሚጥር በመሆኑ፣ ኢትዮጵያ ይህን ከመሰለው የዓለም ቤተሰብ ድርጅት ተለይታ ብቻዋን መኖር አይገባትም በማለት፣ ከዛሬ ሰባት ዓመት ጀምሮ ብዙ ደክመን የአባልነት መብቷን አስገኝተናል። ስለዚህም፣ የማህበርተኛነቷን መብት በሚገባ ለመጠቀምና ለነፃነቷ ዋስትና ይዛ ለመኖር፣ ዓለም የሚከተለውን ዘመናዊ አስተዳደር መሥርታ ሕዝቦቿን ወደ ሥልጣኔ ለመምራት፣ ለማህበሩ

የገባችበት ቃል ኪዳን ያስገድዳታል። ይህንንም ቃል ኪዳን በተግባር ለማሳየት የሚቻለው፤ ዋናው መሠረት የሆነውን ሕገ መንግሥት ማቆም ስለሆነ፤ ጊዜ ሳይባክን ግቡን ለመምታት መፍጠን ያስፈልጋል። በእኛ በኩል ቀደም ብለን እንደነገርናችሁ፤ አገራችን በረዥሙ ዘመን ታሪኳ እስከ ዛሬ ያላየችውን ይህን የአስተዳደር ሕገ መንግሥት ለማቆም ቆርጠን ስለተነሣን፤ የምታስቡትን ሁሉ እንድታስታውቁን እንጠይቃችኋለን። .... »

በስብሰባው ላይ ተካፋይ የሆኑት ሁሉ ይህን ከንጉሠ ነገሥቱ የቀረበላቸውን መግለጫ ካዳመጡ በኋላ፤ "ሐሳብዎ መልካም ነው" ብለው ድጋፋቸውን የሰጡት ጥቂቶች ነበሩ። የአብዛኛዎቹ መሳፍንትና መኳንንት አስተያየት፤ « ... ለኢትዮጵያ አስተዳደር፤ የፈረንጆቹን አሠራር መቅዳት፤ ከአባቶቻችን ሲያያዝ የመጣውን አኩሪውን ልማዳችንንና ሃይማኖታችንን የሚያበላሽ ከመሆኑ በስተቀር፤ የሚሰጠን ጥቅም ይኖራል ብለን አናስብም። .... » የሚል ስለሆነ፤ በዚህ በመጀመሪያው ቀን ስብሰባ ላይ ድጋፋቸውን መስጠት አልፈለጉም። የእነዚህም መሳፍንትና መኳንንት አቋም የተመሠረተው በሚከተሉት ዋና ነጥቦች ላይ ነበር።

1ኛ/ የኢትዮጵያን ሕዝብ በሥነ ሥርዓት ለማስተዳደርና የአገራችንንም ነፃነት ከውጭ ጠላት ጠብቆ ለማቆየት፤ "ፓርላማ" የተባለ አዳራሽ ሠርቶ የአማካሪዎች ስብሰባ በማብዛት ፍሬ ይገኝበታል ብለን አናምንም።

2ኛ/ ሕዝባችን ኑሮው የሰላምና የጸጋ እንዲሆንለት፣ ፍርድ እንዳይጓደልበት፣ እንዳይታረዝና እንዳይራብ፣ የምናስብለትና የምንደክምለት እኛ ስለሆንን፤ ወደፊት መንግሥትን የሚያማክርለትና ችግሩንም መንግሥት እንዲያውቅ የሚያደርግለት፤ ከእኛ የቀረበ ማን አለውና ? .... የተለየ አማካሪ ይቋቋምለታል ?

3ኛ/ እስከዛሬ ድረስ፤ ሕዝባችንን በሰላም ስናስተዳድረው የኖርነውና የአገራችንንም ነፃነት ሳናስነካ የቆየነው፤ የራሳችን የሆነውን ልማዳዊውን ሥርዓትና መሠረታዊውን ባህላችንን በመጠበቅ ነው እንጂ፤ የፈረንጆቹን ምሳሌ እየተከተልን ወይም እየቀዳን አይደለም።

4ኛ/ ይህን ደግ የሆነውን ሕዝባችንን፤ ለንጉሠ ነገሥቱና ለአገሩ ደህንነት ፈጣሪውን እየለመነ፤ ለገዥዎቹ እየታመነና እያገለገለ በሰላም ከሚኖርበት እያፈናቀልን፤ ሳይወድ በግድ በተንኮል የተመረዘውን የፈረንጆች ጠባይ ካልተቀበልክ ብለን፤ እንዳናበላሸው በብርቱ መጠንቀቅ ያስፈልጋል።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ ተዘርዝሮ እንደተገለጸው አብዛኛዎቹ መሳፍንትና መኳንንት፤ የሕገ መንግሥት አስፈላጊነት ስላልታያቸው፤ የሚቃወሙበትን ምክንያት በመደርደር፤ ንጉሠ ነገሥቱ ሐሳባቸውን እንዲሰርዙ ለማድረግ ሞክረው ነበር። ይሁን እንጂ ከመካከላቸው ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ የወሎ ገዥ፣ ፊታውራሪ ብሩ ወልደገብርኤል የጦር ሚኒስትር፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደመስቀል ታሪኩ የጽሕፈት ሚኒስትር፣ የተቃዋሚዎቹን የመሳፍንት ወገን ትተው፤ ደጋፊዎች ከሆኑት ከፕሮግሬሲስት ሚኒስትሮች ከእነ ብላቴን ጌታ ሕሩይ ወልደሥላሴና ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ጋር ስለቆሙ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በሐሳባቸው ጸንተው ለመግፋት የሚያበረታታ መንገድ አገኙ።



ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፤ የሰላሌና የበጌምድር ገዥ፤
የዘውድ ምክር ቤት ሊቀመንበር

ልዕልት ጽጌማርያም በሻህ
የልዑል ራስ ካሣ ባለቤት

በዚህም መሠረት፣ ኢትዮጵያ ከነበረችበት ጥንታዊና ልማዳዊ አመራር፣ ወደ ዘመናዊው አስተዳደር እንድትሸጋገር የሚያስፈልገው ሕገ መንግሥት፣

1ኛ/ የንጉሠ ነገሥቱ ዘውድ አወራረስ ከሣህለሥላሴ እና ከቀ.ኃ.ሥ የትውልድ መስመር ሳይወጣ ከልጅ ወደ ልጅ እንዲተላለፍ የሚወስን፣

2ኛ/ የኢትዮጵያን ሕዝብና የግዛት አንድነት የሚያረጋግጥ፣

3ኛ/ የማዕከላዊውን የንጉሠ ነገሥት መንግሥት ሥልጣን የሚያጠናክር

4ኛ/ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት እስካሁን በልማድ ሲጠቀምበት ከኖረው ከፍጹም ፊውዳላዊ አመራር፣ ወደ ባለሙሉ ሥልጣን ዘውዳዊ አስተዳደር ተሻግሮ በተወሰነ ደረጃ በሕዝብ ምክር ቤት አስተያየት እየታገዘ የሚሠራ፣

5ኛ/ ፓርላማው፣ የሕዝብን መብትና ግዴታ የሚመለከቱትን መሠረታዊ ጉዳዮች እያጠና በሕግ እንዲደነገጉ፣ ለንጉሠ ነገሥቱ ሐሳብ ለማቅረብ እንዲችል፣

በአዋቂዎች ተጠንተው የቀረቡትን እነዚህን መመሪያዎች ንጉሠ ነገሥቱ ካጸደቁ በኋላ፣ በእነዚህ በአምስቱ ዋና ዋና ነጥቦች ላይ ተመስርተው ዝርዝሩን ሕገ መንግሥት እንዲያዘጋጁ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሚከተሉትን ዋና ዋና ታላላቅ ሰዎች መረጡ።

| | |
|---|---|
| 1. ራስ ካሣ ኃይሉ | የቤገምድርና የሰላሌ ገዥ፣ |
| 2. ራስ ኃይሉ ተክለሃይማኖት | የጉጃም ገዥ፣ |
| 3. ራስ ሥዩም መንገሻ | የትግሬ ገዥ፣ (በከፊል) |
| 4. ራስ ጉግሣ አርዓያ | የትግሬ ገዥ፣ (በከፊል) |
| 5. ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ | የወሎ ገዥ፣ |
| 6. ፊታውራሪ ብሩ ወልደገብርኤል | የጦር ሚኒስትር፣ |
| 7. ደጃዝማች ወልደጻድቅ ጉሹ | የአገር ግዛት ሚኒስትር፣ |
| 8. ደጃዝማች ይገዙ በሀብቴ | የቀድሞ የምኒልክ ሚኒስትር፣ |
| 9. ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደመስቀል ታሪኩ | የጽሕፈት ሚኒስትር፣ |
| 10. ብላቴን ጌታ ሕሩይ ወልደሥላሴ | የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር፣ |
| 11. በጅሮንድ ተክለሐዋርያት ተክለማርያም | የገንዘብ ሚኒስትር፣ |

እነዚህ አስራ አንድ አባሎች በአፄ ምኒልክ ቤተመንግሥት ውስጥ በተለይ በተዘጋጀላቸው አዳራሽ፣ በራስ ካሣ ሊቀመንበርነት፣ በየዕለቱ እየተሰበሰቡ የሕገ መንግሥቱን ዝርዝር ጉዳይ ሲያጠኑ፣

1ኛ/ ንጉሠ ነገሥቱ ለየክፍለ ሀገሩ ስለሚያደርገው የአገረ ገዥዎች አሿሿምና እነሱም ስለሚኖራቸው ሥልጣን፣

2ኛ/ የሕግ መምሪያ ምክር ቤት አባሎች ሆነው የሚመረጡት ሰዎች፤ አንዳንድ የሕዝብን መብት በሚመለከቱ ጉዳዮች ላይ ጥናት በማካሄድ፤ በሕግ እንዲደነገጉ ለንጉሠ ነገሥቱ ሐሳብ ያቀርባሉ ስለሚለው አንቀጽ፤

አባሎቹ በሁለት ወገን ተከፍለው ለመስማማት ሳይችሉ ቀሩ። ይህም አለመግባባት ሊደርስ የቻለው፤ ከጥንት ጀምሮ ሲሠራበት የቆየው፤ ልማዳዊው የፌዎዳል አመራር ዝሙን ይዞ እንዲቀጥል በሚፈልጉት መሳፍንትና፤ የተሻለ ዘመናዊ አስተዳደር እንዲመሠረት በሚደግፉት መኳንንት መካከል የሐሳብ ልዩነት በመፈጠሩ ነበር። በዚህ ጉዳይ የእያንዳንዱ ወገን ትክክለኛ አቋም ምን እንደነበረ ዝርዝሩን መመልከት አስፈላጊ ከመሆኑም በላይ፤ በዚያን ዘመን አገራችን የነበረችበትን ሁኔታ ለመገንዘብ የሚረዳ ይሆናል።

## የመሳፍንት ወገኖች አቋም፤

ኢትዮጵያ ! ነፃነትን ጠብቆ በመኖር ሆነ ክርስትናን በመቀበል፤ ከዓለም ነገሥታት ሁሉ የቀደመች፤ የራስዋ በሆነውም ሥልጣኔዋና ባሕሏ በዓለም ታሪክ ላይ ምን ያህል እንደተደነቀች፤ ሳይማሩና ሳይረዱ የሚኖሩ ብዙ ሰዎች እንዳሉ ደህና አድርገን እናውቃለን። ከነዚህም መካከል አንዳንዶቹ የፈረንጆቹን አገር አይተናል፣ ቋንቋቸውንም በመማር ብዙ ነገሮች አውቀናል በማለት ተነሳስተው፤ ለመንግሥታችን አመራርና ለሕዝባችን አኗኗር ጨርሶ የማይስማማ ሐሳብ እያቀረቡ ሲያስቸግሩ በማየታችን እጅግ አድርጎ አሳዝኖናል።

እነዚህ፤ የፈረንጆቹን ምክር የሚከተሉት ሰዎች፤ እስከዛሬ ድረስ ሕዝባችን በምን ወግና ደንብ ሲተዳደር እንደኖረ፤ ገዥዎች ለሕዝባቸው ያላቸውን ፍቅር፤ ሕዝቡም ለገዥዎቹ ያለውን አክብሮትና ታማኝነት ሳይመለከቱና ሳይመዝኑ፤

1ኛ/ ሕገ መንግሥት ሲቆም የገዥዎች አሿሿም እንዲለወጥና ልጅ የአባቱን ግዛት ከመውረስ እንዲታገድ፤ አጥብቀው ጠይቀዋል።

2/ የፓርላማ አማካሪዎች እየተባሉ ከያለበት ተመድበው አዲስ አበባ የሚሰበሰቡት ሰዎች፤ ባልተረዱትና በማያውቁት ጉዳይ፤ ስለ ሕዝብ መብት ተሟጋቾችና ሕግ አውጭዎች መሆን አለባቸው ብለዋል።

ለእኛ እንደታየን፤ የፈረንጅ አድናቂዎች የሆኑት ጥቂቶች መኳንንትና ሚኒስትሮች ያቀረቧቸው እነዚህ ሁለት ሐሳቦች፤ ከብዙ መቶ ዓመታት ጀምሮ በሰላምና በጸጋ ተደስቶ የሚኖረውን ሕዝባችንን፤ የሚያበጣብጡና ከፍተኛ አደጋ ላይ የሚጥሉ መሆናቸውን እንዲገነዘቡት ማድረግ አለብን።

ስለዚህ፤

1ኛ/ በአገር አስተዳደር ጉዳይ፤ እንደ ሕዝባችን ጠባይና ልማድ ኢትዮጵያ በልዩ ልዩ አውራጃዎች ተከፍላ፤ ግዛቱ ለየመሳፍንቱ እየተሰጠ፤ ከእነሱም በኋላ ለልጆቻቸውና ለልጅ ልጆቻቸው እየተላለፈ ከጥንት ጀምሮ ሲሠራበት የኖረው ልማድ እንዲቀጥል፤

2ኛ/ ከመንግሥት በኩል ለሕዝቡ ስለሚደረግለት ቸርነትና ሕዝቡም በበኩሉ ለመንግሥት ስለሚኖረው ግዴታ፤ አስፈላጊውን ደንብ ማዘጋጀት የገዥዎች ሥልጣን ስለሆነ፤ የፓርላማ አማካሪዎች የሚሆኑት ሰዎች በተጠቀሰው ጉዳይ ላይ እያጠኑ የሕግ ሐሳብ ያቀርባሉ የተባለው ጨርሶ እንዲሰረዝ፤ ያስፈልጋል ሲሉ፤ የመሳፍንት ወገኖች አቋማቸውን አጠነከሩ።

## የፕሮግሬሲስቶቹ አስተያየት

የመሻሻል ደጋፊዎች የሆኑት ጥቂቶች መኳንንትና ሚኒስትሮች፤ በሕገ መንግሥቱ ረቂቅ ዝግጅት ላይ የተጠቀሱትን እነዚህን ሁለት አንቀጾች፤ መሳፍንቱ እንቀበልም ስላሏቸው፤ የመከላከያ አስተያየታቸውን ያቀረቡት በሚከተለው አኳኋን ነበር።

እጅግ የተከበራችሁ መሳፍንት አሁን የገለጻችሁልንን ሐሳብ እኛ እንደተረዳነው፤ ኢትዮጵያ በየትልልቁ አውራጃ የምትከፈለው፤ በጥንቱ አመራር መሠረት ግዛቱ ለየመሳፍንቱ እንዲሰጥና ኋላም ለልጅ ልጅ የሚተላለፍ ርስት እንዲሆን ነው። እንዲሁም በየአውራጃው ያሉት ባላባቶች የያዙት መሬት ሁሉ ርስት ሆኖላቸው፤ ቀጥታ ለየመሳፍንቱ ገዥዎች እየገበሩ እንዲኖሩ አስፈላጊነቱን አሰምታችሁናል።

እንግዲህ ! በዚህ በምናዘጋጀው በአዲሱ ሕገ መንግሥት ውስጥ የሚሰፍረው ሐሳብ፤ እጅግ የተከበራችሁት መሳፍንት በተናገራችሁት መልክ ከሆነ፤ አገራችን ወደ ዘመናዊው አስተዳደር መሻገር የለባትም ማለት ነው። በዚህ መንፈስ፤ ዓለም የሚጠቀምበትን መንገድ እየተከተልን መሠልጠን አያስፈልገንም ከተባለ፤ እንደ ጥንቱ ዘመን ድንበራችንን አጥረን፤ በራችንን ዘግተን፤ በጨለማ ውስጥ የለመድነውን ኑሮ ለመቀጠል እንድንችል፤ ሕገ መንግሥት አያስፈልገንም ብሎ ጉዳዩን ባጭሩ መዝጋት ይሻላል። አለበለዚያ፤ የውጭ ጠላት ተነሥቶ ኢትዮጵያውያኖችን ማሠልጠን ያስፈልጋል በሚል ሰበብ ነፃነታችንን ለመግፈፍ ዕድል እንዳንሰጠው፤ በሌላ በኩል ደግሞ ለሕዝባችን ሥልጣኔ ተዘርግቶለት የተሻለ ሕይወት እንዲያገኝ አስፈላጊነቱን ካመንበት፤ እስካሁን ይዘነው የኖርነውን ልማድ ወደ ዘመናዊ አስተዳደር መለወጥ ግዴታችን ይሆናል።

ዛሬ በአለንበት ዓለም ላይ፤ ክቡራን መሳፍንት የምታምኑበት የአገዛዝ ደንብ በሙሉ ተለውጧል። የአገር አስተዳደር ሥልጣን እንደግል ንብረት ለዘር የሚተላለፍ መሆኑ ጨርሶ ከተወገደ ዘመን የለውም። ልጅ የአባቱን ሀብት እንዲወርስ ጥንታዊውም ሆነ ዘመናዊው ሕግ ይፈቅድለታል። ነገር ግን፤ አባቱ ይዞት የነበረውን ሥልጣን በቀጥታ የመውረስ መብት የለውም። ከአባት ወደ ልጅ የሚተላለፈው የነገሥታቱ ዘውድ ብቻ ነው። ስለዚህ፤

1ኛ/ በምናዘጋጀው በአዲሱ ሕገ መንግሥት፤ ንጉሠ ነገሥቱ ለኢትዮጵያ ልዩ ልዩ አውራጃዎች የሚሾሟቸው የሕዝብ አስተዳዳሪዎች፤ ጌቶቻችን እንዳስረዳችሁን፤ ከአያት እስከ ቅድመ አያት ያለው የመሳፍንት ትውልዳቸው እየተቆጠረ ሳይሆን፤ በአስተዳደር ችሎታቸውና በትክክለኛ ፍርዳቸው፤ በመልካም ምግባራቸውና በጨዋነታቸው የሚመረጡ ሰዎች መሆን አለባቸው ብለን፤ ያቀረብነው ሐሳብ እንዲለወጥብን አንፈልግም።

2ኛ/ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ ከየአውራጃው በሕዝቡ ስም ለፓርላማ የሚመረጡት አማካሪዎች፣ « .... የሕዝቡን መብት በሚመለከቱ አንዳንድ መሠረታዊ ጉዳዮች ላይ ጥናት እያደረጉ ንጉሠ ነገሥቱ ሕግ አድርጎ እንዲያጸድቀው ሐሳብ ያቀርባሉ። .... » የሚለውን አንቀጽ፣ ክቡራን መሳፍንት ስለማትቀበሉት ጨርሶ መሰረዝ አለበት ብላችኋል። በዚህም በሚሰረዘው አንቀጽ ምትክ፣ መንግሥት ለሕዝቡ ስለሚያደርገው ቸርነትና ሕዝቡም በበኩሉ ለመንግሥትና ለገዥዎቹ ስለሚኖርበት ግዴታ፣ ደንቡ ስለሚዘጋጅበትና ለንጉሠ ነገሥቱም ቀርቦ ስለሚጸድቅበት ሁኔታ ኃላፊነቱ የአገረ ገዥው መሆኑ እንዲጠቀስ ጠይቃችኋል።

በእኛ በታናናሾቻችሁ አስተያየት፣ ዓለም በሥልጣኔ እጅግ በገሰገሰበት ዘመን፣ መንግሥት በሕዝብ እየተመረጠ፣ ለሕዝብ አገልጋይ ሆኖ ግዳጁን ከመፈጸም በስተቀር፣ ለሕዝብ የሚያደርገው ቸርነት የለም። መንግሥት በመልካም አስተዳደሩ፣ ሕዝቡ ትክክለኛ ፍርድ እንዲያገኝ ቢያደርግ፣ የልማት ሥራዎችንም እያፋጠነ የየአውራጃው ኤኮኖሚ ቢንቀሳቀስና የሕዝቡን ሕይወት ለማሻሻል ቢችል፣ መንግሥት ተግባሩን በሚገባ እንደፈጸመ ተቆጥሮ ምሥጋና ያገኛል እንጂ፣ ለሕዝቡ ቸርነት አደረገ አይባልም። እንዲያውም፣ በአንዳንዶቹ በሥልጣኔ በተራቀቁት አገሮች፣ መንግሥት ለሕዝቡ መሥራት ያለበትን ሁሉ በትክክል ካልፈጸመና የሕዝቡን ፍላጐት ማርካት ካልቻለ፣ ሥልጣኑን እንዲለቅ ይገደዳል።

በአሁኑ ጊዜ፣ እኛ በሥልጣኔ እጅግ የገፉት አገሮች የሚተዳደሩበትን ደንብ እየቀዳን፣ የአገራችን ሕዝብ ሊጠቀምበት ይችላል ለማለት አንቃጣም። እዚህ ደረጃ ለመድረስ ብዙ ጉዞና ብዙ ድካም እንደሚጠይቀን ስለምናውቅ፣ የምናቀርበው የመሻሻል ሐሳብ ከአቅማችን በላይ እንዲሆን አናደርግም። ይሁን እንጂ፣ ማንኛውም ነገር የሚጀመረው ከመነሻው አንድ ተብሎ ስለሆነ፣ ንጉሠ ነገሥታችን ከልባቸው ላሰቡበት ለሥልጣኔው መንገዳችን፣ ይህን ፓርላማ ማቋቋም የመጀመሪያው ዓይነተኛ እርምጃ መሆኑን ሁላችንም በአንድነት መቀበል አለብን። ለዚህም ፓርላማ ሕዝቡ በቀጥታ እንደራሴዎቹን መርጦ ለመላክ፣ በአሁኑ ጊዜ አቅሙም ችሎታውም ስላልፈቀደለት፣ የየአውራጃው ገዥዎችና ባላባቶች፣ በስሙ ሆነው ወኪሎቹን እንዲሠይሙለት ይሻላል ተብሏል። እንግዲህ ! እነዚህ በየአውራጃው ባሉት ታላላቅ ባለሥልጣኖች አማካይነት የሚመረጡት የፓርላማ አባሎች፣ የሚወክሉትን ሕዝብ ችግር እያጠኑ፣ መንግሥት አንዳንድ ማሻሻያ እንዲያደርግ ሐሳብ የማቅረብ መብት ቢኖራቸው ምን ነውር አለበት ? ስለዚህ፣ በእኛ አስተያየት ይህን ጉዳይ የሚመለከተው አንቀጽ እንዲሰረዝ አንስማማም።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ፕሮግሬሲስቶቹ የሰጡት አስተያየት ቀደም ሲል ከቀረበው የመሳፍንት አቋም እጅግ የተለየ ሆነ። አሁን ደግሞ ይህን የፕሮግሬሲስቶቹን አስተያየት፣ መሳፍንት በጥንቃቄ ካደመጡ በኋላ፣ ሳይውል ሳያድር ከኮሚቴው ሊቀመንበር ከራስ ኃይሉ ካሣ የተሰጠው መልስ፣ የነበረውን የሐሳብ ልዩነት በይበልጥ የሚያራርቀው ሆነ እንጂ የሚያቀራርበው መሆን አልቻለም። በተለይም በንግግራቸው ጥራትና በእምነታቸው ጽኑነት እጅግ የታወቁት መስፍን ራስ ካሣ ኃይሉ፣ በጓደኞቻቸው ስም ሆነው በሰጡት መልስ፣ በሥልጣኔ የተራመዱትን የፈረንጆቹን አስተሳሰብና የእነሱንም መንፈስ በመከተል የኢትዮጵያ ፕሮግሬሲስቶች ያቀረቡትን የሕገ መንግሥት ሐሳብ፣ መቃወም ብቻ ሳይሆን ምን ያህል ለማራከስ እንደፈለጉ በግልጽ አሳይተዋል።

## ከመሳፍንት የተገለጸ አስተያየት፤

ራስ ካሣ ኃይሉ

ይህንን የሕገ መንግሥት መቆም ጉዳይ አጥንተን እንድናቀርብላቸው ንጉሠ ነገሥታችን ከመረጡን ሰዎች መካከል፤ እናንተ ጥቂቶቻችሁ ገንጠል ብላችሁ የምትናገሩትን ስናዳምጥና ሐሳባችሁም ወዴት እንደሚያመራ ስናስተውል፤ እጅግ የሚያስገርም ሆኖ አግኝተነዋል። ከአንድም ሁለት ጊዜ ካቀረባችሁት ሐሳብ እንደተረዳነው፤ የሕዝብ ተቆርቋሪዎችና ለሕዝብ አሳቢዎች እኛ ብቻ ነን ለማለትም ይቃጣችኋል።

**ኸረ ለመሆኑ እዚህ ከተሰበሰብነው ማሕል፤**

- **ማንነው ? ለሕዝቡ ዘወትር የሚያስብና ደህንነቱን የሚመኝ፤**
- **ማንነው ? የሕዝቡን ችግር የሚረዳና በቅርብ የሚያውቅ፤**
- **ማንነው ? ሕዝቡን አቅፎ አብሮ የኖረ፤**

ብላችሁ ብታስቡበት፤ ከእናንተ ከጥቂቶቻችሁ በስተቀር፤ ሌሎቻችን በሙሉ በአገራችን አስተዳደር ታውቀን፤ በሕዝባችን ተወደንና ተከብረን የምንኖር መሆናችንን ለመረዳት አያቅታችሁም ነበር። ነገር ግን በእኛና በምናስተዳድረው ሕዝብ መካከል ያለውን ፍቅርና መተማመን አናውቅም ብላችሁ፤ እኛን ለሕዝብ የማናስብ፤ ክፉ ገዥዎች አድርጋችሁ የምትቆጥሩን ከሆነ፤ በአንድ ገበታ ላይ ተሰብስበን ለትልቁ የአገር ጉዳይ አብረን መሥራት የለብንም። ደግሞም ለሕዝብ የቆምን ነን ብላችሁ ወገን ከለያችሁ፤ የመንግሥት ባለሥልጣኖች፤ የመንግሥት ሚኒስትሮችና መኳንንት መሆን የለባችሁም። ወደፊት በሚቆመው በዚህ በአዲሱ ሕገ መንግሥት፤ የመንግሥትና የሕዝብ ተወካዮች በሁለት ምክር ቤቶች ስለሚከፈሉ፤ የሚቀበላችሁ ካገኛችሁ የሕዝብ ወገን እንድትሆኑ፤ በጓዳ ሳይሆን በአደባባይ አስታውቃችሁ ጓዛችሁን ይዛችሁ ወደዚያው ማምራት ነው። እኛ ግን ከአያት ከቅድመ አያታችን ጀምሮ ገዥዎችና የገዥዎች ወገን መሆናችንን ትናንትም ሆነ ዛሬ፤ ነገም ሆነ ወደፊት ከመናገር ወደ ኋላ አንልም። እናንተም የተገዥዎች ወገን ነን የምትሉትን በጓዳ ውስጥ ሳይሆን በአደባባይ ወጥታችሁ እንደ እኛው መናገሩን ድፈሩበት።

ንጉሠ ነገሥቱ ለኢትዮጵያ ስለሚያቆሙት ሕገ መንግሥት ጉዳይ በተለይ በገለጣችሁልን ሐሳብ ውስጥ፤ እናንተ በጠየቃችሁት ዓይነት አንቀጾቹ ካልተደነገጉ፤ ኢትዮጵያ መሠልጠን አትፈልግም በማለት የውጭ ጠላት መጥቶ ይወጋናል። ነፃነታችንን ይወስድብናል። ቅኝ አድርጎ ይገዛናል። እያላችሁ፤ በመደጋገም ልታስፈራሩን ፈልጋችኋል። እኛ በአገር ጉዳይ ባለን ኃላፊነትና በደረስንበት ደረጃ ይህን በመሳሰለ ዛቻ አንሸበርም። እናንተም የዚህን ዛቻ ፍሬቢስነት በትክክል እንድትረዱት፤ እቅጩን (እውነቱን) እንነግራችኋለን። የፈረንጅ ጠላት (ጣልያንም ሆነ ሌላው) አገራችንን በጦር ወግቶ ነፃነታችንን በመግፈፍ ሊገዛን የሚፈልገው፤ ለጥቅሙ ሲል ነው እንጂ፤ ለምን የፈረንጆቹን ሥልጣኔን አልተከተላችሁም ? ብሎ አይደለም። ፈረንጅ ቅኝ ግዛቱ አድርጎ ሊይዘን የሚመኘው፤ ሀብታም አገር በመሆናችን፤ መሬታችንን እያለማ ምርቱን እያስፋፋ፤ ከብቱን በሰፊው እያረባ፤ በማዕድን የሚገኝ ወርቃችንን ሁሉ እየሰበሰበ፤ ወደ አገሩ ለመውሰድና ለሕዝቡ የተቀማጠለ የምቾት ኑሮ ለማደላደል ነው።

ስለዚህ፣ የፈረንጆቹን ሥልጣኔ አሜን እያልን እየተቀበልን፣ እነሱ በሚሰጡን ትምህርት ብቻ እየተመራን ካልሠራን፣ ነፃነታችንን ይገፋታል እያላችሁ እኛን ለማሥጋት የምትጥሩበትን ምክንያት አልተቀበልነውም። ፈረንጆች አገራችንን በኃይል ለመያዝ የሚነሱብን ሀብታችንን በመፈለግ ነው እንጂ፣ የእነሱን ሥልጣኔ ባለመከተላችን ነው ብለን እንደማናምንበት ደጋግመን ተናግረናል። ይህንንም የምንለው፣ እኛ የእነሱን ሥልጣኔ ተከታዮች ብንሆን፣ ምንም ዓይነት ጥቅም እንደማይሰጣቸው ስለተረዳነው ነው። እርግጥ ! ለሁላችንም የሚታየን አንድ የማይታበል ነገር አለ። ከሌሎቹ ፈረንጆች ይልቅ፣ የአድዋውን ቂም መርሳት የማይችለው ጠላታችን ጣልያን፣ ምንጊዜም እንደማይተኛልን ስለምናውቅ፣ ለትጥቁ ዘወትር ዝግጁ መሆን እንዳለብን ሁላችንም ብንስማማ ማለፊያ ይሆናል። ከዚህ ውጭ ግን፣ ካደረባችሁ ከንቱ ሥጋት እንዲያላቅቃችሁ፣ ፈጣሪያችንን ከመለመን በስተቀር በሌላ ልንረዳችሁ አንችልም።

ሁለተኛ ልናስረዳችሁ የምንፈልገው፣ ስለ ትልልቆቹ የአውራጃ ገዥዎች አሿሿም ነው። በዚህ ጉዳይ ላይ የምታስቡትን ደህና አድርገን ተረድተነዋል። በአንድ በኩል፣ የመሳፍንት ልጆች የአባቶቻቸው ግዛት የነበረውን ሊሾሙ አይችሉም ብላችሁ ማገጃ ታደርጉና፣ በሌላ በኩል ደግሞ ንጉሠ ነገሥቱ ለዚህ ሹመት የሚመርጧቸው ሰዎች፣ በጨዋነታቸው የተከበሩ፣ በአስተዳደርና በፍርድ ሥራ ችሎታ ያላቸው መሆን አለባቸው ትሉናላችሁ። ታዲያ! እናንተ እንደምትሉት፣ እነዚህ ተሿሚዎች በጨዋነታቸው የታወቁ፣ የፍርድ አሰጣጥና የአስተዳደር ችሎታ ያላቸው መሆን ካለባቸው፣ እነዚህን የመሳሰሉትን ታላላቅ ሰዎች ማግኘት የሚቻለው ከመሳፍንትና ከመኳንንት ቤተሰብ ውስጥ ካልሆነ በስተቀር፣ ከሌላ፣ የት ቦታ መፈለግ የሚቻል ይመስላችኋል? እኛ እንደሚመስለን፣ እናንተ የምትጠሉት፣ " መሳፍንት " የተባለውን ሥያሜ ከሆነ፣ የምትወዱት ደግሞ " ጨዋ " የሚባለውን መጠሪያ ከሆነ፣ እናንተን ደስ ለማሰኘት፣ ለየአውራጃዎቹ ገዥዎች ንጉሠ ነገሥቱ የሚሾሟቸው <u>የጨዋ ልጆች</u> እንዲሆኑ፣ በሕገ መንግሥቱ እንዲጠቀስ ፈቃዳችን ይሆናል።

ቀጥሎ ደግሞ የምንነግራችሁ፣ ከየአውራጃው ፓርላማ ለተባለው ነገር ስለሚመረጡት አማካሪዎች ጉዳይ ነው። በአገረ ገዥው ሙሉ ሥልጣንና በረዳቶቹ አማካይነት፣ ከየአውራጃው እየተደለደሉ አዲስ አበባ የሚሰበሰቡት ሰዎች፣ የሕዝብን ጉዳይ በሚመለከት ነገር ሕግ የማዘጋጀት ሥራ አላቸው ብላችሁ ያቀረባችሁትን ሐሳብ አንቀበለውም ብለናችሁ ነበር። እናንተ ግን ሐሳባችሁን እንለቅም ብላችሁ ሙግቱን መቀጠል ፈልጋችኋል። በዚህ ጉዳይ በረዥሙ መነጋገር ጊዜን ከማባከን በስተቀር ፍሬ ያለው ውጤት ይገኝበታል ብለን እናስብም። ሆኖም፣ የኛ አስተያየት በጣም ግልጽ መሆኑን እንድትረዱት ደግመን እንናገራለን። ከየአውራጃው እየተመረጡ በፓርላማው አዳራሽ የሚሰበሰቡት ሰዎች፣ መንግሥት ለሕዝቡ አስተዳደርና አኗኗር በየጊዜው እያሰበ የሚያዘጋጀውን ደንብ፣ አማካሪዎቹ መክረው የሚመስላቸውን አስተያየት እንዲሰጡ በሚጠየቁበት ጊዜ መናገር ነው እንጂ፣ እነሱ በየግላቸው ተነሳስተው ሕግ እያዘጋጁ፣ እንዲደነገግላቸው ሽቅብ ወደ ላይ የሚያቀርቡ መሆን የለባቸውም። ሳንስማማበት እስከአሁን የቆየው ይኸ ጉዳይ ይህንን ያህል ግራ የሚያጋባ አልነበረም። የጐደለው ጉዳዩን ላይ ላዩን እንደ ፈረንጅ አስተያየት በመጋለብ ሳይሆን በረጋ መንፈስ ጠለቅ አድርጎ ማየቱ ነው። እነዚህ የፓርላማ አማካሪዎች፣ ከያለበት የሚመረጡት በመንግሥት በኩል ሲሆን፣ ሥራ የሚሰጣቸው ከመንግሥት መሆኑንና በዚህ ሥራም እስከሚቆዩ ድረስ ኃላፊነታቸው ለመንግሥት መሆኑን ደህና አድርጎ

መገንዘብ ያስፈልጋል። በእኛ አስተያየት፤ መንግሥት ለሕዝቡ በሚያስበውና በሚሠራው ጉዳይ፤ ቅን ምክር እንዲሰጠው የተመደበ የፓርላማ አማካሪ፤ ድንበሩን አልፎ የትዕዛዝ ዓይነት የሆነ ሕግ አዘጋጅቶ እንዲያቀርብ መንገድ መስጠት አይገባም።

ከመካከላችሁ፤ አንድ ወይም ቢበዛ ሁለት የምትሆኑት ሰዎች፤ ይህን እኛ የምንለውን ሐሳብ፤ እንኳንስ ለመቀበል ለማመዛዘንም ቢሆን ፈቃዳችሁ እንደማይሆን ይታየናል። ይህም ሊደርስ የቻለው፤ የአገራችንንና የሕዝባችንን ጉዳይ ከመሠረቱ ደህና አድርጋችሁ ባታጠኑት ይመስለናል። የሆነ ሆኖ ከእኛ መካከል፤ ለሕዝቡ ሰላምና ኑሮ የሚያስብ እንጂ፤ የሕዝብን ጥቅም የሚፃረር፤ ከዚህም በላይ ሕዝቡን የሚወድ እንጂ ሕዝቡን የሚጠላ አለመኖሩን እንድትረዱት እንፈልጋለን።

የስብሰባው መሪና የመሳፍንቱ ሐሳብ ገላጭ የሆኑት ልዑል ራስ ካሣ ስላደረጉት ንግግር፤ ለፕሮግሬሲስቶቹ እንደ አፈጉባኤ የሚቆጠሩት በጅሮንድ ተክለሐዋርያት ተክለማርያም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የገንዘብ ሚኒስትር፤ መልስ ለመስጠት ተነሡ።

ጌታዬ ራስ፤ ለንግግርዎ ማሰሪያ ያደረጉት፤ ከመሳፍንቱ ወገን ሕዝብን የሚበድልና ሕዝብን የሚጠላ የለም ብለው ነው። እኔና ወዳጆቼ ይህን አስተያየት ለመቀበል እንቸገራለን። እንዲያውም ቢፈቅዱልኝ አንቀበለውም ማለትን እመርጣለሁ። እርግጥ ! በእናንተም በኩል ችግር መኖሩን እናውቃለን። ግዛታችሁ እጅግ ብዙ ስለሆነ፤ ለየክፍሉ የምትሾሟቸው እንደራሴዎቻችሁ በገባሩ ሕዝብ ላይ ምን ያህል በደል እንደሚያደርሱ፤ ምን ያህል ግፍ እንደሚፈጽሙ በትክክል ላታውቁ ትችላላችሁ። የሕዝቡን ችግር ማየት የሚችለው፤ የሕዝብ ቤተሰብ የሆነውና ከሕዝቡ አጠገብ የሚኖረው ብቻ ነው። ስለዚህ፤ ገዥዎች በሕዝቡ ላይ ከሚያዘንቧቸው መከራዎች አንዳንዶቹን፤ በዘመናዊ አስተዳደር ሥርዓት ለመቀነስ እንዲቻል፤ አዲሱ ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕገ መንግሥት ለማቆም እርምጃ በመውሰዳቸው፤ ሁላችንም ከልባችን ልናመሰግናቸው ይገባል።

ይህ የሚዘጋጀው ሕገ መንግሥት፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ በዘር ሥሪት ሆነ በሹመት፣ በጌትነት ሆነ በድህነት፣ ሳይከፋፍል ለሁሉም እኩል የሆነ መብት የሚሰጥ መሆን አለበት። አለበለዚያ ጌታዬ ራስ ቀደም ሲል እንደገለጹት፤ ለኢትዮጵያ አስተዳዳሪዎች የሚመረጡት፤ ከመሳፍንት ልጅ፣ ከጨዋ ልጅ፣ ከመኳንንት ልጅ እየተፈለገ ከሆነ፤ መጨረሻችን ምን እንደሚሆን ማሰብ ያስፈልጋል። ይህ ዓይነቱ አስተሳሰብና አሠራር፤ ለዛሬው እንኳ ባይሆን ለነገው፤ ቂምን አጠራቅሞ ለክፉ በቀል ዝግጁ እንደሚያደርግ መታወቅ አለበት። ይህን የመሳሰለው ችግር በዓለም ላይ ባለፉት ዘመናት ደርሶ የታየ ስለሆነ፤ ታሪኩን በማንበብ ወይም በመስማት ትምህርቱን መውሰድ ያስፈልጋል። ስለዚህ፤ ሕዝብንና መንግሥትን አቀራርቦ አገርን ለማልማት እንዲቻል፤ የጥንቱን አስቸጋሪውን ልማዳችንን ትተን፤ በዘመናችን የተገኘውን የዴሞክራሲ ጥበብ እንድንጠቀምበት መጣር ግዴታችን ይሆናል። በዚህ መሠረት፤ እስካሁን ሲያከራክሩንና ሳንስማማባቸው የቆየንባቸው እነዚህ ሁለቱ የሕገ መንግሥት አንቀጾች፤ ለእኛና እኛን ለመተካት በማደግ ላይ ለሚገኘው ትውልድ ምን ያህል ቁም ነገሮች መሆናቸውን የሁላችንም ዕምነት እንዲሆን አቤቱታዬን አላቋርጥም። በተጨማሪም ጌታዬ ራስ ቢፈቅዱልኝ፤ ቀደም ሲል ያቀረብኩትን ሐሳብ ማብራራትና ደጋግሜ ማሳሰብ እፈልጋለሁ። ባለፈው ጊዜ ስናገር፤ ለየአውራጃው የሚሾሙት ገዥዎች፤

በአስተዳደር ችሎታቸውና በጨዋነት ምግባራቸው የሚመረጡ መሆን አለባቸው ያልኩት፤ እናንተ እንደምታስቡት የመሳፍንት ልጅ፣ የጨዋ ልጅ የሚባሉትን አለመሆኑን በቃለ ጉባኤው እንዲመዘገብልኝ አጥብቄ እለምናለሁ።

ጌታዬ ራስ እንደሚያውቁት፤ በአሁኑ ሰዓት እኔ ራሴ በመንግሥት ዘንድ ታዋቂ ሆኜ፤ የገንዘብ ሚኒስትርነትን ሥልጣን የተቀበልኩት፤ በትምህርቴና በችሎታዬ ተመርጬ ነው እንጂ፤ የጨዋ ልጅ፤ የመኳንንት ልጅ ነህ ተብዬ አይደለም። እኔም ተሾምኩ ተከበርኩ ብዬ፤ መሠረተ ትውልዴን በምንም ምክንያት አልለውጥም። ከአንድ ጥሮ አዳሪ ቤተሰብ የተወለድኩ መሆኔን እኮራበታለሁ።

ለኢትዮጵያ ኃላፊነትን ለሚቀበለው መሪ በኢትዮጵያዊነት ግዳጁ ለማገልገል የምቀርበውም፤ ለአገራችን ዕድገት፤ ለሕዝባችን ደህንነት የሚጥር፣ የሚያስብና የሚሠራ ሆኖ ሳገኘው ነው እንጂ፤ በውርሱ ንጉሥ፣ በዘሩ መሥፍን ነው ብዬ አይደለም። ያለፈው ታሪኬ በትክክል እንዳሳየው፤ ልጅ ኢያሱ አጉል ጠባያቸውን አሻሽለው ኢትዮጵያን ከነክብሯ በሰላም እንዲመሯት ብዙ ደክሜ ሳይሆንልኝ ሲቀር፤ ለለውጡ ከሸዋ መኳንንት ጋር የተሰለፍኩት፤ ኢትዮጵያን የምወድ፣ ለኢትዮጵያ የቆምኩ በመሆኔ ብቻ ነው። ዛሬም እኔና ጓደኞቼ የምንመካውም ሆነ የምንኮራው በኢትዮጵያ ላይ ብቻ ስለሆነ፤ ኢትዮጵያንና ሕዝቧን በቅንነት ከማገልገል ሌላ የሚያረካን ነገር አይኖርም። ጌታዬ ራስ፤ ብዙ በመናገሬ ይቅርታዎን እለምናለሁ።

<u>የራስ ካሣ መልስ፤</u>

አሁን በጅሮንድ ተክለሐዋርያት የተናገርከውን ሁሉ በጥሞና አዳምጠናል። ሐሳብህም ከእኛ ጨርሶ የራቀ መሆኑን አስረድተሃል። የአንተ ሐሳብ ከእኛ ጋር ለመቻውም እንደማይገጣጠም እኛ የምናውቀው ገና ዛሬ አይደለም። ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ነው። ደግሞም የራስህ የሆነውን ሐሳብ፤ እባክህ? ከእኛ ጋር አቀራርበው ብለን አልጠየቅንህም። ወደፊትም አንጠይቅህም። ብቻህንም ሆነ ወይም ጓደኞቼ ከምትላቸው ጋር ሐሳብህን ይዘህ መኖር ትችላለህ። መቻም መብት የሚባለው ነገር ይኸ ይመስለኛል። ይልቁንስ አንድ ምልክት ያደረግነው ነገር፤ እኛ ያላልነውንና ያላሰብነውን እየጨማመርክ መናገርህን ነው። ይኸ የተገባ አይደለም።

እኛ፤ አንተ የሌለብህን በግዴታ የጨዋ ልጅ ነህ፣ የመስፍን ወገን ነህ አላልንም። የጨዋነትን ጉዳይ ያመጣኸው አንተው ራስህ ነህ። ባለፈው ቀን ስትናገር፤ ለአገረገዥነት ሹመት አንድን ሰው እጩ የሚያደርገውን መለኪያ ስትቆጥር፤ ትልቁ ቁም ነገር ጨዋነቱ ነው ብለህ ነበር። በዚያን ጊዜ እኛም ሐሳብህ ማለፊያ መሆኑን አይተን፤ ጨዋ የሆኑ ሰዎች የት እንደሚገኙ ሠፈሩን ለይተን ነገርንህ እንጂ፤ ሌላ ታሪክ ውስጥ አልገባንም። ከልብህ የሚሰማህን አውጥተህ በጋለ መንፈስ ስትናገር፤ በኢትዮጵያዊነትህ መኩራትህና መመካትህ ደስ የሚያሰኝ ነው። ይህችንም የምትመካባትን ኢትዮጵያ ከታወቀው የሚያኮራው ታሪኳና ባህሏ ጋር፤ ነፃነቷን ጠብቀው ያቆዩልን ነገሥታቷ አንተ የምትጠላቸው መሳፍንቶች ሕዝባቸውን ይዘው ሲቀበሉት የኖሩትን መስዋዕትነት ልትስተው አትችልም። ይልቁንም ልታከብረው ይገባል። ስለዚህ፤ በኢትዮጵያዊነት የሚኮሩ፣ በኢትዮጵያዊነት የሚመኩ፣ ነገሥታቱና መሳፍንቱ፣ መኳንንቱና ባላባቱ ከሕዝቡ ጋር አብረው የሚቆጠሩ ናቸው እንጂ፤ ለብቻ ተነጥለው የሚታዩ አይደሉም።

አንተ መቸም በመሳፍንትና በጨዋው መኳንንት ላይ የተለየ አመለካከት እንዳለህ እናውቃለን። ይሁን እንጂ፤ መሳፍንቱንና መኳንንቱን ከሕዝቡ እየለየህ የምታሳየው ጥላቻ ተገቢ አለመሆኑን አንድ ቀን ትገነዘበው ይሆናል። " የራሱን ጥሎ የሰው አንጠልጥሎ " እንደተባለው፤ አንተስ ብትሆን ኢትዮጵያዊነቱን የሚወድና ከልቡም ኢትዮጵያን የሚያገለግል የሚገኘው፤ ከእኔና ከጓደኞቼ መካከል ነው እያልክ ለመናገር ስትደፍር፤ በአገር ጉዳይ በእኛና በአንተ መሰሎች መካከል ልዩነት መፍጠርህን እንዴት ትዘነጋዋለህ ? .... ኧረ ለመሆኑ ኢትዮጵያ ያንተና የመሰሎችህ ብቻ መሆኗን፤ ቅን አገልጋይዎቿም አንተና መሰሎችህ ብቻ መሆናችሁን የፈረደው ማነው ? .... እኛ በረዥሙ ታሪካችን ከሕዝባችን ተለይተን አናውቅም። እስከ ዛሬም ኢትዮጵያን እያገለገልን የኖርነው ከሕዝባችን ጋር ነው። ነፃነቷን ለመጠበቅ ስንደማላትና ስንሞትላት የኖርነውም ከሕዝባችን ጋር ሆነን ነው። ስለዚህ፤ እኛን ለአገር እንደማንሠራ፣ ለሕዝቡ እንደማናስብ፣ ሕዝቡም እኛን እንደማይፈልግ እያስመሰልክ አግድም አግድሙን የምትናገረው ሁሉ ሳይገርመን አልቀረም። መሠረተ ታሪክህን ደጋግመህ ነግረኸናል። ምንም እንኳ ከድሃው ቤተሰብ መወለዴ ያኮራኛል እያልክ ደስታህን በሞቀ አኳኋን ብትገልጥም፤ እንደ ልጃቸው ያሳደጉህ አባትህ ራስ መኰንን እና እናትህ ወይዘሮ የሺእመቤት ናቸው። አፄ ምኒልክን ለምነው፤ ፈረንጅ አገር ልከው ለአያሌ ዘመናት ያስተማሩህ ራስ መኰንን ናቸው። አሁንም ደግሞ፤ የተማርክ ሊቃውንት ነህ፤ ለአገርህ ትጠቅማለህ ብለው ለሚኒስትርነት ያበቁህ፤ የአባትህ የራስ መኰንን ልጅ ተፈሪ መኰንን ናቸው። **እንግዲህ ! ለአንተ የደረሰውን ዕድል ልብ ብለህ ካስተዋልከው፤ ከዚህ የተሻለ መኳንንትነት የት ይገኝ ይመስልሃል ? ስለዚህ፤ መኳንንት ነኝ ብትል፤ ተቀባይ እንደማታጣ ማወቅ አለብህ።** እኔ ይህን ሁሉ የምናገረው፤ በልቤ የማስበውንና የማምንበትን እንድታውቀው ነው እንጂ፤ አንተ በመሳፍንት ቤተሰብ ላይ እንዳለህ ጥላቻ፤ እኔም በአንተ ላይ ቂም አሳድሬ አይደለም። ይህንን እንድትረዳልኝ አደራ እልሃለሁ።

እንግዲህ ! እስከአሁን ድረስ የተወያየነው ይበቃናል። የሕገ መንግሥቱን ጉዳይ ብዙውን ሠርተን ስናበቃ፤ በሁለት ጉዳዮች ላይ ብቻ ሁላችንንም የሚያስማማ መድኃኒት ሳናገኝለት ቀርተናል። **እነዚህም፤ አንደኛው፤ ስለ አውራጃ ገዥዎች አሿሿም ሲሆን፤ ሁለተኛው ለፓርላማ የተመረጡት ሰዎች ስለሚኖራቸው ሥራ ነው።** በእነዚህ በሁለቱ ጉዳዮች ላይ በሁለት የተከፈለውን ሐሳባችንን፤ ንጉሠ ነገሥቱ አይተው ዳኝነት እንዲሰጡበት፤ ከጽሕፈት ሚኒስቴር የመጡልን ቃል ተቀባዮቻችን <u>አቶ ተክለማርቆስና አቶ ገብረወልድ</u> ማስታወሻቸውን በቶሎ አዘጋጅተው እንዲያቀርቡ ይሁን። በዚህ ከንጉሠ ነገሥታችን የተሰጠን ሥራ ከሞላ ጐደል ተፈጽሟል ማለት ነው። ሁላችንም ከልባችን የሚቻለንን ሁሉ ማድረጋችንና መድከማችን የሚካድ አይደለም። በስብሰባችን ላይ ስንነጋገር፤ አለመስማማትና አለመጣጣም ደርሶብናል። ይኸ መቸም የአገር ጉዳይ የሆነ ሥራ ሲሠራ፤ የሚያስከትለው ችግር ነው። ከዚህም የተነሳ በአንዳንድ ጉዳይ በሐሳብ መከፋፈላችን ለጊዜው በመካከላችን ቅሬታ ያሳደረ መስሎ ቢታይም፤ ወዳጅና ጠላት አድርጎ የሚለያየን መሆን የለበትም። ይኸን ሳንስማማ የቀረንበትን ነገር ንጉሠ ነገሥቱ መርምረው ውሳኔ በሚሰጡበት ዕለት፤ ጉዳያችን ይዘጋል። .... **በሚል ቃል ሊቀመንበሩ ራስ ካሣ ኃይሉ ስብሰባውን በተኑ።***

* ቃለ ጉባኤ፤ አቶ ተክለማርቆስና አቶ ገብረወልድ ጽሕፈት ሚኒስቴር 1923 ዓ.ም

## የንጉሠ ነገሥቱ ውሳኔ፤

በልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ ሊቀመንበርነት የተሰበሰቡት አባሎች ባልተስማሙባቸው ሁለት አንቀጾች ላይ፤ አንድ ውሳኔ መስጠት አስፈላጊ ስለሆነ፤ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው የሚመሩት ጉባኤ ተደረገ። ስምምነት ከታጣባቸው ከእነዚህ ከሁለቱ ጉዳዮች ውስጥ እጅግ አጨቃጫቂ የሆነው፤ ለየአውራጃዎቹ ስለሚደረገው የገዥዎች አሿሿም እንደነበረ ይታወሳል።

መሳፍንቱ፤ ቀደም ሲል በኮሚቴው ላይ በገለጹት ሐሳብ በመጽናት፤

1ኛ/ ኢትዮጵያ በዋና ዋና ትልልቅ አውራጃ ተከፍላ፤ ከጥንት ሲያያዝ በመጣው ልማድ መሠረት፤ ግዛቱ ለየመሳፍንቱ እንዲሰጥና ከእነሱም በኋላ ለልጅ ልጅ የሚተላለፍ እንዲሆን፤

2ኛ/ በውስጣቸውም ያለው የየአውራጃው ባላባት፤ የያዘው ግዛት ርስት ሆኖለት፤ ለመሳፍንቱ እየገበረና እየታዘዘ እንዲኖር፤

በሕገ መንግሥቱ ተጽፎ መግባት አለበት ሲሉ የጠነከረ አቋም ያዙ።

ፕሮግሬሲስት የሆኑት ወገኖች ደግሞ፤ የኢትዮጵያ ግዛት ለመሳፍንትና ለባላባት እየተከፋፈለ ለልጅ ልጅ የሚተላለፍ ርስት ሆኖ ከተሰጠ፤ ሕዝቡ ኢትዮጵያን አገሬ ነች ለማለት እንዴት ይችላል ? የሚል ጥያቄ ካቀረቡ በኋላ፤ ይህ ዓይነቱ አስተሳሰብ ቀጥታ የፍጹም ፌውዳልን አሠራር የሚከተል ስለሆነ፤ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ መግባት የለበትም ብለው ምሬታቸውን ገለጡ።

እንግዲህ ! ልማዳዊውን የፌውዳል ሥርዓት በሚያምኑት መሳፍንትና፤ ዘመናዊ አስተዳደር እንዲመሠረት በሚደግፉት ሚኒስትሮች መካከል በተፈጠረው ከፍተኛ የሐሳብ ልዩነት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ለሚሰጡት ውሳኔ ምን ያህል ከባድ እንደሆነባቸው መገንዘብ ይቻላል። ንጉሠ ነገሥቱ በዚያን ጊዜ የነበራቸው አስተሳሰብ በፕሮግሬሲስት መንፈስ ላይ የተመሠረተ ቢሆንም፤ የዘውዳቸው ምሰሶዎች ከሆኑት ከመሳፍንቱና ከባላባቱ ጋር፤ ቀጥታ የሆነ ጦርነት መግጠም አይችሉም ነበር። ማንንም ሳይፈሩ ፊት ለፊት ሐሳባቸውን የሚገልጡትን የበጅሮንድ ተክለሐዋርያትንና እንዲሁም የራስ እምሩን ድጋፍ ተመርኩዘው፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመሳፍንቱን ሐሳብ ውድቅ አድርገዋለሁ ቢሉ፤ ምንም እንኳ እንደ ልጅ ኢያሱ ከሥልጣን ሊያወርዷቸው ይችላሉ ባይባልም፤ የሚመሩት መንግሥት ታዛዥና ተቀባይ እንዲያጣ፤ በያለበት ለማሳደም በቂ አቅም እንደነበራቸው ማሰብ ያስፈልጋል።

ስለዚህ፤ ንጉሠ ነገሥቱ በቀረበላቸው በሁለት ተቃራኒ ሐሳቦች ላይ፤ ሁለቱም ወገኖች ሊስማሙበት የሚችሉበትን መንገድ በዘዴ ለማግኘት ከመሞከር በስተቀር፤ በመጀመሪያ ደረጃ ብዙ ምርጫ አልነበራቸውም። ፕሮግሬሲስቶቹ የንጉሠ ነገሥቱን መጨነቅና አስቸጋሪ በሆነ አቋም ላይ መገኘታቸውን አይተው፤ የሚከተሉትን የማሻሻያ ሐሳቦች አቀረቡላቸው።

1ኛ/ እስከአሁን ድረስ ያሉት መሳፍንትና ባላባቶች፣ ጥፋት ካልተገኘባቸው በስተቀር፣ የተሾሙባቸውን ግዛታቸውን ይዘው ለመቆየት እንዲችሉ፣
2ኛ/ እነዚህ ገዥዎች ጥፋት ተገኝቶባቸው ቢሻሩ፣ ወይም ቢሞቱ፣ በምትካቸው የሚሾመውን ሰው ንጉሠ ነገሥቱ የሚመርጠው በዕውቀቱና በችሎታው እንጂ፣ በትውልድ እንዳይሆን፣

3ኛ/ የመሳፍንት ተወላጅ የሆኑት ሁሉ፣ ምንም እንኳ በቀጥታ የአባቶቻቸውን ግዛት እንዳይወርሱ በሕግ ቢከለከሉም፣ ዕውቀታቸውና የሥራ ችሎታቸው በቂ ሆኖ ከተገኘ፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንደ ማንም ኢትዮጵያዊ መብታቸውን ጠብቆ፣ የአገረ ገዥነት ሹመት እንዲሰጣቸው፣እንስማማለን አሉ።

መሳፍንቱም ይህንን ከሚኒስትሮቹ የቀረበውን ሐሳብ ካደመጡ በኋላ፣ እነሱም በበኩላቸው አንድ መጠነኛ የሆነ ማሻሻያ ለማድረግ ሞከሩ፡ ይኸውም፣ ከመላው የኢትዮጵያ አውራጃዎች ውስጥ፣ ሥሪታቸው የመሳፍንት ግዛት ሆኖ ለብዙ ዘመናት የታወቁት፣ አንዳንዶቹ አውራጃዎች ብቻ እየተመረጡ፣ ከአባት ወደ ልጅ ይተላለፋሉ ተብሎ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ ከተጻፈ፣ ለተቀሩት ግዴለንም የሚል ነበር። ፕሮግሬሲስት የተባሉት መኳንንትና ሚኒስትሮች ደግሞ፣ የደጋፊዎቻቸው ቁጥር እየጨመረ መሄዱንና የመሳፍንቱም አቋም ወደ መዳከም ማዘንበሉን ሲያዩ፣ የበለጠ በመጠናከር የቀረበላቸውን የማሻሻያ ሐሳብ በፍጹም አንቀበልም አሉ። በዚህ ጊዜ፣ ሁለቱን ወገኖች የሚያቀራርብና የሚያስማማ መንገድ አለመገኘቱ ግልጽ ሲሆን፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የዳኝነት ሚናቸውን ትተው፣ የራሳቸውን አቋም በመውሰድ የሚከተለውን ተናገሩ።

ሁላችሁም እንደምታውቁት፣ ይኸን ከብዙ ዓመታት ጀምሮ ስናስብበት የነበረውን ሕገ መንግሥት ለማቆም እርምጃ የወሰድነው፣ አገራችን ኢትዮጵያ ከጨለማው ኑሮ ወደ ብርሃን ተሸግራ፣ የዓለም መንግሥታት የሚጠቀሙበትን ዘመናዊ አስተዳደር አግኝታ ወደ ሥልጣኔ እንድትገዝ ነው። ይህን በማድረግ ለአገራችን ብዙ ጥቅም እንደሚገኝበት ሁላችንም የምናምንበት ከሆነ፣ እስከዛሬ ተጭኖን የኖረውን የፌዎዳል አሠራር ለመለወጥ መተባበር አለብን።

የፌዎዳል ሥርዓት በዓለም ላይ እጅግ የተወገዘና የተፋቀ ስለሆነ፣ ለእኛ ለሥልጣኔያችን ጠቃሚያችን የሆነውን ሕገ መንግሥት በታሪካችን ለመጀመሪያ ጊዜ ስንመሠርት፣ ይኸው የተጠላው የፌዎዳል አሠራር ካልተጨመረበት ብለን ሳንስማማ ብንቀር፣ ወዳጆቻችን በሆኑት በዓለም መንግሥታት መሪዎች ዘንድ ምን ያህል ትዝብት እንደሚወሰድብንና፣ ጠላቶቻችንንም እንደምናስደስት ማወቅ አለብን። በዚህ ጉዳይ በመሳፍንቶቻችንና በሚኒስትሮቻችን መካከል የተፈጠረውን አለመግባባት ልብ ብለን ከተመለከትነው፣ በውነቱ ይህን ያህል የሚያጣላንና የሚያለያየን ሆኖ አናየውም። ለልዩ ልዩዎቹ የኢትዮጵያ አውራጃዎች፣ የገዥዎች አሿሿም በይዞታና በዘር መተላለፉ ቀርቶ፣ በዕውቀትና በችሎታ መምረጥ ይሻላል ብለው ሚኒስትሮቻችን ያቀረቡት ሐሳብ፣ መሳፍንትና መኳንንት ችሎታ ቢኖራቸውም ለገዥነት አይመረጡም ማለት አይደለም። በእኛም አስተያየት ዕውቀትና ችሎታ የተራው ሕዝብ መብት ብቻ ሆኖ፣ የመሳፍንትን ልጆች እየለየ ለሹመት የሚያግድ እንዲሆን አንፈቅድም። በዚህም አኳኋን የመሳፍንት ልጆች ዕውቀታቸውና የአስተዳደር ችሎታቸው በቂ ሆኖ ከተገኘ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ሹመቱን አይነፍጋቸውም የተባለው ትክክል ነው። ከዚህም በቀር፣ አንዳንዶቹን የኢትዮጵያ

አውራጃዎች በማቅናት የታወቁትንና ከፍተኛ አገልግሎት የሰጡትን መሳፍንቶች፣ ንጉሠ ነገሥቱ በተለይ ውለታቸውን እየመዘነ፣ ለልጅ ልጅ የሚተላለፍ የመስፍንነት ርስተ-ጉልት ሊተክልላቸው ይችላል ተብሎ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ እንዲጸፍ የተጠየቀውን እንፈቅዳለን። ነገር ግን፣ የአገሪ ገዥዎችን እሿሿም በሚመለከተው ጉዳይ የሆነ እንደሆነ፣ ንጉሠ ነገሥቱ መርጦ የሚሾማቸው ከመሳፍንቱም ሆነ ከሌላው ወገን ችሎታቸው የተመሰከረላቸውን ብቻ እንጂ፣ በትውልድ የሚተላለፍ ሹመት እንዳይኖር የተባለውን፣ ሁላችንም ልንደግፈው ይገባናል።

ሁለተኛው ሳትስማሙበት ተንጠልጥሎ የቆየው ጉዳይ፣ ከየአውራጃው የሚመረጡት የሕግ መምሪያ ምክር ቤት አባሎች የሕዝቡን ችግር በሚያውቁት መንገድ እያጠኑ፣ የማሻሻያ ሕግ ለማዘጋጀት ይችላሉ ስለተባለው ነገር ነው። በዚህ ጉዳይ መስማማት ያልተቻለው በምን ዓይነት የሀሳብ ልዩነት እንደሆነ በጅሮንድ ተክለሐዋርያት ማስረጃውን እንዲያቀርብልን እንጠይቀዋለን።

<u>በጅሮንድ ተክለሐዋርያት</u>፣ ይህን ጉዳይ እኔ እንዳስረዳ ጃንሆይ የጠየቁኝን በደስታ እቀበላለሁ። ሁላችንም እንደምናውቀው፣ ጃንሆይ በፈቃድዎ ለኢትዮጵያ የሚያቆሙት ሕገ መንግሥት፣ የሕግ መወሰኛና የሕግ መምሪያ ምክር ቤቶች እንዲኖሩት ተደርጓል። የሕግ መወሰኛ አማካሪዎችን (በሠለጠነው ዓለም ሴናተር የሚባሉትን) ከመሳፍንትና ከመኳንንት ከሚኒስትሮችና ከብዙ ታላላቅ ሹማምንቶች መካከል እየመረጠ የሚሾማቸው ንጉሠ ነገሥቱ እንዲሆን ተወስኗል። እነዚህም አማካሪዎች፣ በቅድሚያ ተጠሪነታቸውም ሆነ ኃላፊነታቸው መርጦ ለሾማቸው መንግሥት መሆኑ የታወቀ ነው። የሕግ መምሪያ አማካሪዎችን ግን፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ ችሎታው ተሟልቶለት፣ እንደራሴዎቹን በቀጥታ ለመምረጥ እስከሚችልበት ጊዜ ድረስ፣ የየአውራጃው ገዥዎችና ሹማምንቶች በስሙ ሆነው እንዲመርጡለት ተደርጓል። ይሁን እንጂ፣ ለእነዚህ አማካሪዎች የሚሰጣቸው ኃላፊነት፣ የሕዝብ ተወካይነትን ደረጃ የያዘ ነው እንጂ፣ እንደ ሕግ መወሰኛ አባሎች የመንግሥት ሹሞች ሆነው የሚቆጠሩ አይደሉም። ስለዚህም፣ እነዚህ በሕዝብ ስም የተመረጡት አማካሪዎች፣ በኖሩበት አውራጃ በቅርብም ሆነ በሩቅ የሚያውቁትን አንዳንዱን የሕዝብ ችግር እያጠኑ፣ መፍትሔ ሆኖ የሚታያቸውን የማሻሻያ ሕግ አዘጋጅተው ንጉሠ ነገሥቱ እንዲያጸድቅላቸው፣ ማመልከት ይችላሉ ብለን ያቀረብነውን ሐሳብ፣ ክቡራን መሳፍንት ለመቀበል ፈቃዳቸው ሳይሆን ቀርቷል። በሌላ በኩል ደግሞ፣ በንጉሠ ነገሥቱ የሚሾሙት የሕግ መወሰኛ አማካሪዎች፣ ለመንግሥትና ለሕዝብ ጥቅም የሚሆን ሀሳብ ሲኖራቸው፣ ሕጉን አዘጋጅተው ቢያቀርቡ የተገባ ይሆናል በማለት፣ ክቡራን መሳፍንት ድጋፋቸውን ሲሰጡ አይተናል።

እንግዲህ ! ግርማዊነትዎ እዚህ ላይ እንዲያዩት የሚያስፈልገው፣ በክቡራን መሳፍንት አስተያየት፣ በሚቋቋሙት በሁለቱ ምክር ቤቶች መካከል ልዩነት እንዲኖር የሚፈለግ መሆኑን ነው። ይኸውም፣ የመንግሥት ተሿሚዎች የሆኑት የሕግ መወሰኛ አማካሪዎች፣ ሕግን የማመንጨትና የማዘጋጀት መብት ሲኖራቸው፣ ለሕዝብ ተብሎ በሕዝብ ስም የሚመረጡት የሕግ መምሪያ አማካሪዎች ግን፣ ካልተጠየቁ የማይናገሩ፣ ካልቀረበላቸው የማይሠሩ ሆነው፣ ትዕዛዝ ሲቀበሉ ብቻ እንዲኖሩ ተፈርዶባቸዋል ማለት ነው።

ጃንሆይ እንደሚያውቁት፣ በአንድ አገር ውስጥ የዴሞክራሲ ጉዳና የሚቀየሰው፣ ሕዝቡ በእኩል ደረጃ የሚጎዝበት እንዲሆን ነው እንጂ፣ ለትልልቁ ስፊውን፣ ለትንንሹ ጠባቡን መንገድ እየለየ የሚያደላድል መሆን የለበትም። እኔና ወዳጆቼ በኮሚቴው ሥራችን ላይ ከክቡራን መሳፍንት ጋር በድፍረት በብዙ የተከራከርነው፣ በሕግ መወሰኛና በሕግ መምሪያ አማካሪዎች መካከል፣ የታላቅና የታናሽ አመለካከት እንዳይሰጥ ነው። ስለዚህም፣ ሁለቱም ምክር ቤቶች የሚመክሩትና የሚሠሩት፣ መንግሥት ሲጠይቃቸውና ሲያቀርብላቸው ብቻ እየጠበቁ ሳይሆን፣ ለአገሩና ለሕዝቡ ጠቃሚ የሚሆነውን ሁሉ የማጥናትና ሐሳብ የማቅረብ ኃላፊነት በእኩል ደረጃ እንዲኖራቸው ያስፈልጋል። ዞሮ ዞሮ ሁለቱም ምክር ቤቶች የሚያጠኑትም ሆነ አዘጋጅተው የሚያቀርቡት ሕግ፣ በአዋጅ ሊወጣ የሚችለው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ሲያጸድቀው ብቻ ስለሆነ፣ ክቡራን መሳፍንትን የሚያሠጋ ነገር አለመኖሩን ደግሜ ለማረጋገጥ እወዳለሁ።

ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ከንጉሠ ነገሥቱ በተጠየቁት መሠረት ከዚህ በላይ የተገለጸውን ማብራሪያ ከሰጡ በኋላ፣ የመሳፍንቱ ተቀዳሚ የሆኑት ልዑል ራስ ካሣ፣ እኔም የማስረዳው አለኝ ብለው ተነሡ።

ፊታውራሪ ተክለሐዋርያት ዛሬ የገለጸውን ሐሳብ፣ ከዚህ ቀደም በስብሰባችን ላይ እንደዚህ አጣፍጦና ቀባብቶ አልነገረንም። በተለየም አዲስ የሰማነው ነገር፣ ከየአውራጃው እየተመደቡ የሚሰበሰቡት የሕግ መምሪያ አማካሪዎች፣ በራሳቸው አኳኋን እያጠኑ የሚያቀርቡት ሐሳብ፣ ንጉሠ ነገሥቱ ወዶ ካላጸደቀው በስተቀር ሕግ ሆኖ በአዋጅ ሊወጣ አይችልም ብሎ የተናገረው ነው። ይህን ሐሳብ ከዚህ ቀደም እንደዚህ ቁልጭ አድርጐ መናገሩን አናስታውስም። ወይም ደግሞ እሱ ተናግሮት እኛ በቅጡ ሳንረዳለት ቀርተን ይሆናል። ይህንንም የምለው ለወቀሳ አይደለም። .... ለማናቸውም ይህ ዛሬ የሰማነውን ባለፈው ስብሰባችን ሰምተነው ቢሆን ኖሮ፣ የኛን ሐሳብ ካቆምንበት መሠረት የምንለውጠው አይሆንም ነበር። በጅሮንድ ተክለሐዋርያት ዋና ነገር አድርጎ ያስረዳው፣ የመወሰኛ አማካሪዎች ሕግ እያዘጋጁ ለማቅረብ ይችላሉ ሲባል፣ ለመምሪያዎቹ ይኸ ሥራ አይገባቸውም በማለት መሳፍንቱ ተቃውመውናል ብሎ ነው። እውነቱን ነው። መቃወማችን የሚታበል አይደለም። ስንቃወም ግን ምክንያታችንን ደህና አድርገን አስረድተን ነው። በጅሮንድ ይህን ከመናገር ቀጥቦ ቢያስቀረውም፣ እኛ ዛሬ በጃንሆይ ፊት ደግመን ለማስረዳት አይቸግረንም። ለመወሰኛ አማካሪዎች የሚሆኑትን ንጉሠ ነገሥቱ መርጦ የሚሾማቸው፣ በመስፍንነትና በሚኒስትርነት፣ በዳኝነትና በጦር አለቅነት፣ መንግሥትን ለብዙ ዘመናት ካገለገሉት ውስጥ ነው። እንግዲህ፣ እነዚህ ሁሉ መኳንንት፣ ስለ አገራችን ታሪክ፣ ስለ መንግሥታችን አመራር፣ ስለ ሕዝባችን አስተዳደር፣ ደህና አድርገው የሚያውቁ በመሆናቸው፣ በአማካሪነታቸው ለመንግሥትና ለሕዝቡ የሚጠቅሙትን አንዳንድ ሕጐች እያዘጋጁ ቢያቀርቡ፣ ተገቢ መሆኑን የሚስተው የለም። ነገር ግን ለመምሪያው ምክር ቤት የመንግሥታችን ሹማምንቶች፣ እየመረጡ የሚልኳቸው ሰዎች፣ በየአውራጃው ታዋቂ ከሆኑት ከገበሬዎችም ሆነ ከነጋዴዎች መካከል ስለሆነ፣ ስለ መንግሥት አመራር፣ ስለ ሕዝብ አስተዳደር፣ ስለ ዳኝነት አሠራር የሚያውቁት ምንም ነገር እንደሌለ ለሁላችንም ግልጽ ነው። ስለዚህ፣ እነዚህን ሰዎች ባላወቁትና ባልለመዱት ጉዳይ ለመንግሥት ማስተዳደሪያ የሚሆን ሕግ እያዘጋጃችሁ አቅርቡ ብሎ ማስቸገር፣ በእኛ አመለካከት የተገባ ሆኖ አላገኘነውም። ቀደም ብለን እንደገለጽነው ይህንን ሐሳባችንን ባለፈው ስብሰባችን ተናግረነው ነበር። ስላልተደመጥን ይኸው ዛሬም

ደግመነዋል። ጃንሆይ ያዘዙን የምናምንበትንና የሚታየንን ምክር እንድናቀርብ ነው። ውሳኔው የጃንሆይ ብቻ ነው። የእኛ ሥራ እዚህ ላይ ይቆማል።

ከዚህ በላይ እንደቀረበው፣ የበጅሮንድ ተክለሐዋርያት ማብራሪያና የራስ ካሣ ንግግር፣ በመሳፍንቱና በሚኒስትሮቹ መካከል ያለውን የሐሳብ ልዩነትና የሁለቱንም ወገኖች የጠበቀ አቋም ስለሚያሳይ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ውሳኔ ከመስጠታቸው በፊት አሁንም የራሳቸውን አስተያየት በቅድሚያ መግለጽ አስፈልጓቸው ነበር።

ራስ ካሣ ደህና አድርገህ ያስረዳኸን፣ በሕገ መንግሥቱ ከተጻፉት ደንቦች ውስጥ አንዳንዶቹ ለሥራ አፈጻጸም ምን ያህል ችግር እንደሚፈጥሩና ምንም ውጤት መስጠት የማይችሉ መሆናቸውን ነው። ለዚህም ምሳሌ የሚሆነውን ጥሩ አድርገህ እንደገለጽክልን፣ ለሕግ መወሰኛ አማካሪ ሆነው የሚሾሙት ሰዎች፣ ከመሳፍንቱና ከሚኒስትሮቹ፣ ከመኳንንቱና ከጦር አለቆቹ መካከል ስለሆነ፣ እነሱ አጥንተው የሚያቀርቡት ሐሳብ፣ ከችሎታቸው ትልቅነት የተነሣ፣ ለሕዝቡም ለመንግሥቱም ጠቃሚ እንደሚሆን አይጠረጠርም። ለመምሪያው ምክር ቤት የሚመረጡት ሰዎች ግን፣ አንዳንዶቹ በቂ የሆነ የመንግሥት ሥራ ልምድ ስለሌላቸው፣ ሕግ አውጭዎች ትሆናላችሁ ሲባሉ፣ ከባድ ሸክም እንደሚሆንባቸው የነገርከን ሁሉ ትክክል ነው።

ይሁን እንጂ፣ እዚህ ላይ ሁላችንም ልንስማማበት የሚያስፈልግ አንድ ትላቅ ነገር አለ። ይህን ሕገ መንግሥት የምናቆመው በብዙ ሺህ ዓመታት ታሪካችን ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ ስለሆነ፣ ሕዝባችን ጥቅሙ ምን እንደሆነ እስከሚረዳውና እኛም አሠራሩን እስክምንለምደው ድረስ፣ ብዙ አድካሚ የሆነ ውጣ ውረድ እንደሚገጥመን አውቀን መዘጋጀት ይኖርብናል። በእኛ በኩል የዚህ ሕገ መንግሥት መቆም ትላቅ ጥቅም ይሰጠናል ብለን ከምንጠብቀው አንደኛው ቁም ነገር፣ ለሥልጣኔው መንገዳችን መረማመጃ እንደሚሆነን ስለምናስብ ነው። ዛሬ በአለንበት ዘመን፣ የሠለጠኑት አገሮች የሕገ መንግሥታቸውን አመሠራረት የተመለከትን እንደሆነ፣ መንግሥትን ለማቆም፣ መንግሥትን ለመሻር፣ የመንግሥትን ሥራ ለመቆጣጠር ሙሉ ሥልጣን ያለው ፓርላማው ሆኖ እናገኘዋለን። እኛ እዚህ ደረጃ ለመድረስ የብዙ ዘመናት ድካም የሚጠይቀን ቢሆንም፣ ቅድም በጅሮንድ ተክለሐዋርያት እንዳስረዳው፣ አጀማመራችን የዴሞክራሲን መንገድ የሚከተል ሆኖ እንዲታይ፣ በመወሰኛና በመምሪያ አማካሪዎቻችን መካከል የመደመጥም ሆነ የወንበር ልዩነት እንዳናደርግ መጠንቀቅ አለብን። በዚህ አኳኋን የላይኛውም ሆነ የታችኛው ምክር ቤት አማካሪዎች፣ ለመንግሥት አመራርና ለሕዝብ አስተዳደር ይጠቅማል ብለው የሚያስቡትን አጥንተው በሕግ እንዲደነገግላቸው ማቅረብ ይችላሉ ቢባልም፣ በመጨረሻው ወሳኙ ንጉሠ ነገሥቱ ስለሆነ፣ ምንም ዓይነት ችግር ይደርሳል ብለን አናስብም። በዚህም መሠረት በረቂቁ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ሰላሣ ስድስተኛው ላይ « ... አማካሪዎች ለሕዝብ ጥቅም የሚሆን ሐሳብ ሲያገኙ ለንጉሠ ነገሥቱ ማቅረብ ይችላሉ ... » የተባለውን ፈቅደናል በማለት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመጨረሻ ውሳኔያቸውን ሰጡ።*

---

* የጽሕፈት ሚኒስቴር የተመደቡት ቃለ ጉባኤ ያዥዎች፣ አቶ ተክለማርቆስና አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅ ለበላዮቻቸው ካቀረቡት ሪፖርት የተወሰደ።

## የራስ እምሩ አስተያየት፤

በራስ ካሣ ኃይሉ የተመራው ኮሚቴ አባል የነበሩት ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ (በዚያን ጊዜ የወሎ ገዥ) ስለ ሕገ መንግሥቱ ዝግጅት በማስታወሻቸው ላይ በአጫጭር ቃላት የጠቀሷቸውን አንዳንድ ሁኔታዎች መመልከት ጠቃሚ ይሆናል።

1. አፄ ኃይለሥላሴ ሕገ መንግሥት ለማቆም ባሰቡበት ጊዜ፤ በአገራችን ዘመናዊ ትምህርት ያልተስፋፋ፤ እጅግ ብርቱ የሆነ የንጉሥና የባላባት እንዲሁም የካህናት ሥልጣን የበዛበት ስለሆነ፤ ዴሞክራቲክ የሆነ ኮንስቲቱሽን (ሕገ መንግሥት) ለማዘጋጀት የሚቻል አልነበረም።

2. ለሕገ መንግሥቱ ዝግጅት የተመረጥነው ሰዎች ሥራውን ስንጀምር የቀረበልን ሐሳብ፤ የፌዎዳልነትን መንገድ ብቻ የያዘ፤ ለመሳፍንቱም ከነወራሾቻቸው ከፍ ያለ ሥልጣን የሚሰጥ ነበር።

3. እኔና ወዳጄ በጅሮንድ ተክለሐዋርያት የኮሚቴው አባሎች እንድንሆን በመመረጣችን ደስ አለን። ደስ ያለንም ምክንያት መሳፍንቱ የፈለጉትን እንዳያደርጉ ለመቃወም ቁርጥ ሐሳብ ስለአለን ነው። .... በዚህም መሠረት በየጉዳዩ ላይ መሳፍንቱን በክርክር የገጠምናቸው ሁለታችን ስንሆን፤ ሌሎቹ መኳንንቶች ምንም እንኳ የኛን ሐሳብ ቢደግፉም፤ ደፍረው አይናገሩም ነበር።

4. ከመሳፍንቱ በኩል የቀረበው ሐሳብ ደንበኛ ሕገ መንግሥት አለመሆኑን በጅሮንድ ተክለሐዋርያት እየዘረዘረ ሲያስረዳ፤ « .. እኛ የምንናገረውን ሁሉ እምቢ ብላችሁ እናንተ የምትፈልጉትን ብቻ ብታደርጉ፤ የሚቆያችሁ መጥፎ ታሪክ መሆኑን ማሰብ አለባችሁ .. » ብሎ ተቃወመ። እኔም የእሱን ሐሳብ እየደገፍኩ ልንተባበራቸው አለመቻላችንን እየገለጥኩ እናገር ነበር። መሳፍንቱም፤ እኛ እስከዚህ ድረስ የምንናገር ስላልመሰላቸው ወይም ስላልጠበቁ፤ ንግግራችንን ሲሰሙ እንደ መብረቅ የወደቀባቸው ጩኸት መሰላቸው። ከራሶቹ፤ ማለት ከመሳፍንቱ ወገን ጉዳዩን አጠንክረው የሚፈልጉትን ሁሉ የሚናገሩት ራስ ካሣ ነበሩ። ሌሎቹ የእሳቸውን ሐሳብ ከመደገፍ በስተቀር፤ ብዙ አይናገሩም ነበር።

5. የአፄ ኃይለሥላሴ ሐሳባቸውና ፈቃዳቸው፤ ቀጥታ እንደ እንግሊዝ አገርና ወይም ደግሞ እንደ ጃፓን ሕገ መንግሥት ዓይነት ሳይሆን፤ ከሁሉም ዓይነት ተውጣጥቶ፤ ለኢትዮጵያ ሕዝብና ለንጉሡም እንዲስማማ ስለሆነ፤ ሥራው እጅግ አስቸጋሪ ነበር።

6. የመሳፍንቱ ፍላጐት ግን የጥንቱን አመራርና አሠራር፤ ደንብ አድርጎ ለማዘጋጀት እንጂ፤ ለማሻሻል አልነበረም። እኛም፤ የጥንቱ ሁሉ መቅረት አለበት ብለን ጠንክረን ስንከራከራቸው፤ በመሳፍንቱና በእኛ መካከል ዓይን ለዓይን እንዳንተያይ የሚያደርስ ጠብ ሆኖ ነበር። አፄ ኃይለሥላሴም፤ ከእኛው ወገን በመሆናቸው፤ በእሳቸውና በመሳፍንቱ መካከል የነበረውን ወዳጅነት በጣም ሳያቀዘቅዘው አልቀረም።

7. እኛም በተቻለን መጠን ከመሳፍንቱ ጋር እየተከራከርንበት የሚበዛው የኛ ፍላጐት ተፈጽሞ ሥራችንን ጨርሰን ለንጉሡ ነገሥቱ አስተላለፍን።

# ሕገ መንግሥቱ በይፋ ፀደቀ

ሐሙስ ሐምሌ 9 ቀን 1923 ዓ.ም፤ ከጠዋቱ በአራት ሰዓት በዳግማዊ ምኒልክ ቤተመንግሥት ውስጥ፤

- ንጉሣዊ ቤተሰብና መሳፍንት፣
- ራሶችና ሚኒስትሮች፤
- መኳንንትና ደጃዝማቾች፣
- ጳጳሳትና የቤተክርስቲያን መሪዎች፣
- የጦር አለቆችና ታላላቅ ሹማምንቶች፣
- የውጭ አገር መንግሥታት እንደራሴዎችና ቆንስሎች፤

ተካፋይ እንዲሆኑ በተዘጋጀበት ትልቅ ሥነ በዓል ላይ፤ ለኢትዮጵያ ሕዝብ መተዳደሪያ በታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ የተሰጠውን ሕገ መንግሥት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በፊርማቸው አጸደቁ።

ከዛሬ ስማንያ ዓመት በፊት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ይህን ሕገ መንግሥት ለማዘጋጀት ቆርጠው ሲነሱ፤ በጣት ከሚቆጠሩ፤ በሥልጣኔ ዕድገት ከሚያምኑት ጥቂቶች ሰዎች በስተቀር፤ የአብዛኛዎቹ ታላላቅ ሰዎች ድጋፍ እንዳልነበራቸው ከዚህ ቀደም ሲል የተነበበው የዝግጅቱ የታሪክ ሂደት በትክክል አሳይቶናል። የመሳፍንቱ ተቀዳሚ የሆኑት ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፤ የዚህን ሕገ መንግሥት አመሰራረት ስላላመኑበት፤ ደጋፊዎቻቸውን ይዘው ተቃውሞአቸውን በማጠንከር፤ በአዋጅ እንዳይወጣ ለማገድ እንደሚችሉ ጥርጥር አልነበረውም። ነገር ግን፤ ታላቁ መስፍን በግላቸው ለተፈሪ መኰንን የተለየ ፍቅርና የተለየ አስተያየት ስላላቸው፤ በተጨማሪም ምናልባት ንጉሠ ነገሥቱን እግዚአብሔር አመልክቷቸው ይሆናል በሚል መንፈሳዊ አስተሳሰብ፤ የተጠበቀውን ያህል ተቃዋሚ ሆነው ችግር አልፈጠሩም።

እሳቸው ሊቀመንበር ሆነው በመሩት በዚህ ኮሚቴ ላይ፤ በአባሎቹ መካከል የተፈጠረው የሐሳብ ልዩነት በምን አኳኋን ክርክር ይደረግበት እንደነበረ ሲታይ፤ የዛሬ ስማንያ ዓመት፤ በኢትዮጵያ ንጉሣዊ ፀሐይ ላይ ዴሞክራሲ ለመፈንጠቅ ሞክሮ ነበር ወይ? ሊያሰኝ ይችላል። በተለይም ራስ ካሣ ከደፋሩ ተናጋሪ ከተክለሐዋርያት ጋር የገጠሙት ክርክር፤ ከዚህ ቀደም ታይቶ የማይታወቅ ከመሆኑም በላይ፤ የታወቁት መስፍን ስለ አገርና ሕዝብ አስተዳደር ያላቸውን የጠነከረ ፊዎዳላዊ እምነት በቆራጥነት ሲገልጹ፤ ከተቃዋሚያቸው የቀረበውንም ሐሳብ በእርጋታና በፀጥታ መንፈስ ሲያዳምጡ መታየታቸው፤ እጅግ የሚደነቁ ሆነው ተገኝተዋል።

በዚህ ኮሚቴ ላይ አባሎች ከነበሩት ሚኒስትሮችና መኳንንት መካከል፤ የጦር ሚኒስትሩ ፊታውራሪ ብሩ ወልደገብርኤልና የጽሕፈት ሚኒስትሩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደመስቀል ታሪኩ፤ ምንም እንኳን በስብሰባው ላይ አስተያየታቸውን ባይገልጹም፤ ንጉሠ ነገሥቱ የሚደክሙበትን ሕገ መንግሥት መደገፋቸው የታወቀ ስለሆነ፤ ስልፋቸው ከእነ ራስ እምሩ ጋር ነው ተብሎ ተቆጥሯል። የወሎው ገዥ ራስ እምሩ ኃይለሥላሴ ከመሳፍንቱ መካከል ተገንጥለው፤ በተለይ የተክለሐዋርያት

ደጋፊ መሆናቸውን ሲገልጹ፤ ራስ ካሣን ያለጥርጥር እንደአስገረማቸው ማመን ይቻላል። ለምሳሌም ያህል፤ በጆሮንድ ተክለሐዋርያት በፕሮግሬሲስቶቹ ስም ሆነው ላቀረቡት ሐሳብ፤ ራስ ካሣ መልስ በሰጡ ጊዜ፤ « ... እናንተ ጥቂቶቻችሁ ገንጠል ብላችሁ የምትናገሩትን ሁሉ ስናዳምጥና ሀሳባችሁም ወዴት እንደሚያመራ ስናስተውል፤ እጅግ የሚያስገርም ሆኖ አግኝተነዋል። ... » ሲሉ የተናገሩት፤ ራስ እምሩን የሚመለከት ሳይሆን አይቀርም። ከዚህ በፊት እንደታየው፤ ይህ ሕገ መንግሥት ለመጽደቅ የቻለው በደጋፊዎቹ ቁጥር ብዛት እንዳልሆነ ለማንም ግልጽ ነው። በመጨረሻውም ንጉሠ ነገሥቱ ለውሳኔ ኮሚቴውን በሰበሰቡበት ጊዜ፤ ራስ ካሣ ኃይሉ በራሳቸውና በመሳፍንቱ ስም ሆነው በሰጡት መግለጫ፤ ባልተስማሙባቸው በሁለቱ ዋና ዋና አንቀጾች ላይ፤ አቋማቸውን እንደማይለውጡ አጠንክረው መናገራቸው ይታወሳል። ሆኖም፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወደ እነ ተክለሐዋርያት ሐሳብ በማዘንበል የሰጡትን የመጨረሻ ውሳኔ፤ የታወቁት መስፍን ሳይቃወሙ በዝምታ ማለፋቸው እጅግ የሚያስደንቅ ሆኖ ታይቷል። በዚህ ጉዳይ ላይ ምርምር ሲደረግ፤ ካሣ ኃይሉ ተቃውሞአቸውን ያላቀረቡት፤ ወንድሜ ተፈሪን ለምን ላሳዝነው በሚል ስሜት እንጂ፤ ውሳኔውን የሚያምኑበት አለመሆኑን ብዙ ሰዎች ተናግረዋል። ያም ሆነ ይህ፤ አባ ጠቅል ኃይለሥላሴ፤ ሕገ መንግሥቱን በይፋ አጽድቀው፤ በተግባር እንዲውል አውጀዋል። እንግዲህ አሁን ፓርላማው ሥራውን ከጀመረ በኋላ፤ በአገር ውስጥና በውጭው ዓለም የፈጠረው ስሜት እንዴት እንደነበረ፤ ማስታወስ ያስፈልጋል።

በየአውራጃው የታወቁት ባላባቶችና ያገር ሽማግሌዎች፤ የፓርላማው አባሎች እንዲሆኑ በሕዝቡ ስም መንግሥት እየመረጠ ወደ አዲስ አበባ በሚልካቸው ሰዎች ላይ እምነት አላደረባቸውም። አብዛኛዎቹ ተመራጮች በየአውራጃው ግዛት በምስለኔነትና በወረዳ ገዥነት አርሶ አደሩን ሲያስቃዩና ጉቦ እየተቀበሉ የግል ሀብታቸውን ሲያዳብሩ የሚኖሩ ናቸው በመባል፤ በሕዝቡ ዘንድ እጅግ የተጠሉ ናቸው። የእነዚህ ሰዎች የፓርላማ አባል በመሆን ከየአውራጃው ወደ አዲስ አበባ መዛወር፤ ለገበሬው ሕዝብ እንደ ትልቅ ግልግል የሚቆጠር ቢሆንም፤ በአዲስ አበባ ምክር ቤት አዳራሽ ካባ ለብሰው በኖሩበት ዘመን፤ የሕዝቡን ችግር እያጠኑ ከመንግሥት ጆሮ ለማድረስ፤ ወይም መንግሥት ሕዝቡን የሚጠቅም አንዳንድ ተግባር እንዲፈጽም ሐሳብ ለማቅረብ፤ የሚሞክሩ አይደሉም ተብለው ተስፋ የተቆረጠባቸው ሆነዋል።

እንደተባለውም፤ እነዚህ የምክር ቤት አባሎች፤ አዲስ አበባ መጥተው የፓርላማ ወንበራቸውን ከተረከቡ በኋላ፤ ለጥቅማቸው ቅድሚያ የሚሰጡ በመሆናቸው፤ በየጊዜው ለንጉሠ ነገሥቱና ለመንግሥታቸው ታማኝነታቸውን ከማረጋገጥ በስተቀር፤ በሕዝቡ ላይ የሚደርሰው የአስተዳደር ችግር እንዲቃለል አንዳች ጠቃሚ የሆነ ሐሳብ ሲሰነዝሩ አልታዩም። በጥንታዊው የሕግ መምሪያ ምክር ቤት ቃለ ጉባኤዎች ላይ የሰፈሩትን አንዳንድ የመማክርቱን አስተያየት ስንመለከት፤ እጅግ የሚያስገርሙ ሆነው እናገኛቸዋለን። አብዛኛዎቹ አማካሪዎች በስብሰባ ላይ የሚያቀርቡት ሐሳብ፤ « ... ንጉሠ ነገሥታችን ለሕዝባቸው መልካም አኗኗር ምን ያህል እንደሚጨነቁና ሌት ተቀን እንደሚደክሙ፤ ፓርላማው በሚዘጋበት በክረምቱ ጊዜ ብቻ ሳይሆን፤ በበጋውም ወራት የተወሰኑ ቀናቶች ተሰጥቶን፤ ወደተወከልንበት ግዛት እየተጓዝን ሕዝቡ በትክክል እንዲያውቀው ማስረዳት አለብን ... » የሚል ነው። ከዚህ አስተያየት መገንዘብ የሚቻለው፤ እንደ ሕዝብ ተወካዮች ሆነው የተመረጡት የምክር ቤቱ አባሎች፤ ዋና ተግባራቸው



ንጉሠ ነገሥቱ በፈቃዳቸው የሰጡት የመጀመሪያው ሕገ መንግሥት፤
(ጥቅምት 24/1924)

አድርገው የሚመለከቱት፣ የንጉሠ ነገሥቱንና የመንግሥታቸውን ጥረት ለተወከሉበት አውራጃ ሕዝብ ማስረዳት እንጂ፣ የሕዝቡን ችግርና የሕዝቡን ፍላጐት ወደ መንግሥት ለማቅረብ ሆኖ አይታይም። እነዚህ የሕግ መምሪያ አማካሪዎች በተሰጣቸው ወንበር ላይ ለምን ያህል ዓመት እንደሚቆዩ፣ የሚወስንላቸውና ጥፋትም ከተገኘባቸው የሚሽራቸው ንጉሠ ነገሥቱ ስለሆነ፣ በተቻለ መጠን ለብዙ ዓመታት የአዲስ አበባን የምቾት ሕይወት ለመጠቀም፣ ለመንግሥት ታማኝና ለመንግሥት አሳቢ መስለው ለመታየት የሚጥሩ እንደነበሩ አንዳንዶቹ መረጃዎች አሳይተዋል። ስለዚህም፣ ሕዝብ እንዲወደን፣ ሕዝብ እንዲያከብረን የሚል ዓላማ ሳይኖራቸው፣ የመንግሥት ድጋፍ እያገኙ በሰላም መኖርን የሚመርጡ መሆናቸው የሚያጠራጥር አይደለም።

በውጭውም ዓለም፣ ይህ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መልካም ፈቃድ የቆመው ሕገ መንግሥት፣ ለአገሪቱ አመራር አስፈላጊውን ሥልጣን በሙሉ አጠቃልሎ የሰጠው ለንጉሠ ነገሥቱ ብቻ ስለሆነ፣ ዘመናዊውን የፓርላማ አሠራር ያልተከተለ ነው በማለት፣ በተለይ የአውሮፓ አገሮች የወቀሳ አጐዳ ሲያወርዱበት ኖረዋል። በዚህም አኳኋን የኮሎኒያሊስቶቹ መንግሥታት በየመልኩ የሚሰጡት ትችት በሚከተሉት ነጥቦች ላይ የተመሠረቱ ነበሩ።

1ኛ/ ለፓርላማው፣ ሕዝቡ በቀጥታ እንደራሴዎቹን ለመምረጥ ችሎታው አይፈቅድለትም ተብሎ፣ መንግሥት በሕዝቡ ስም የሚመርጣቸው አማካሪዎች፣ ለቅርጽና ለወግ ካልሆነ በስተቀር፣ የሕዝብ ተወካዮች ነን ብለው የፖለቲካ እንቅስቃሴ ሊያደርጉ አይችሉም።

2ኛ/ በሕገ መንግሥቱ ተዘርዝሮ እንደተገለጸው፣ የምክር ቤቱ አባሎች መንግሥት አስተያየት እንዲሰጡበት የሚጠይቃቸውን ተቀብለው ከመምከር በስተቀር፣ እነርሱ ራሳቸው እርምጃ ወስደው አስተዳደሩን ለመተቸት ሆነ ለመቆጣጠር አይችሉም። በተለይም፣ የንጉሠ ነገሥቱን ሚኒስትሮች ለአስረጅነት ወደ ፓርላማ እንዲመጡ መጥራት አይፈቀድላቸውም።

3ኛ/ የሕግ መምሪያ ምክር ቤት አባሎች፣ ከመካከላቸው ሰብሳቢያቸውን እንኳ መምረጥ ስለማይችሉ፣ ፕሬዚዳንቱንና ምክትሉን፣ እንዲሁም ዋና ጸሐፊውን ጭምር፣ ከውጭ መርጦ የሚሾምላቸው ንጉሠ ነገሥቱ ነው።

እንግዲህ ! እነዚህ ከዚህ በላይ የተጠቀሱትን ሦስት ጉዳዮች ብቻ ይዘው፣ የኮሎኒያሊስቶቹ መንግሥታት በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ላይ የሚያወርዱትን ነቀፌታ ከጊዜ ወደ ጊዜ እያሰፋፉ፣ « ... ምንም ዓይነት ሥልጣን የሌለው ባዶ ፓርላማ ማቋቋሙ ለምን አስፈለገ ? እስከ ማለት ደርሰው ነበር። ነገር ግን የአውሮፓ መንግሥታት፣ እነዚህን የጠቀሷቸውን ሦስት ጉዳዮች ብቻ ይዘው፣ የነቀፌታ ከበሮ ሲደልቁ ከመኖር፣ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ የሰፈሩትን ሁሉ አንድ በአንድ ትኩረት ቢሰጧቸው፣ ለአንድ መንግሥት መሠረታዊና ጠቃሚ የሆኑትን አንዳንድ ቁም ነገሮች ለማግኘት ይችሉ ነበር። ለምሳሌም ያህል፣ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ ንጉሠ ነገሥቱ ለሕዝቡ ስለፈቀደው መብት፣ በምዕራፍ ሦስት ላይ የተዘረዘረውን ቢመለከቱት፣ በኢትዮጵያ ታሪክ ውስጥ ለመጀመሪያ ጊዜ፣ ስለ ዜጐች መሠረታዊ መብቶች፣ ነፃነትና ግዴታዎች በሕግ ተዘርዝረው በመውጣታቸው፣ ለአገሪቱ አንድ ትልቅ እርምጃ ሆኖ ሊቆጠር እንደሚገባው መገንዘብ ይችሉ ነበር። ስለዚህም



ልዑላን መሣፍንትና መኳንንት፤ ሕገ መንግሥቱን ካዘጋጁ በኋላ
በፊርማቸውና በማሕተማቸው አፀደቁት

ጉዳይ፣ በሕገ መንግሥቱ ከአንቀጽ 18 እስከ 28 ድረስ ከተዘረዘሩት የሕዝብ መብቶች ውስጥ፣ ዋና ዋናዎቹን መጥቀስ ተገቢ ይሆናል።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ የሆነ፣ በንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ውስጥ የጦር አለቃ ለመሆንና፣ በጠቅላላውም በመንግሥት ሥራዎች ውስጥ ከፍተኛ ኃላፊነት ሊቀበል ይችላል።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ የሆነ፣ ከአንዱ ሥፍራ ወደ ሌላው ሥፍራ በነፃነት እየተዘዋወረ ለመኖር ይችላል።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ፣ በሕግ መሠረት ይያዛል ! ይፈረድበታል ! ይታሰራል! እንጂ፣ ያለ ሕግ ለመያዝም፣ ሊፈረድበትም ሊታሰርም፣ አይችልም።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ፣ ከሕግ ውጭ፣ ቤቱና ዕቃዎቹ አይበረበሩበትም።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ፣ ከሕግ ውጭ ከማንም ሰው ጋር የሚጻጻፈው ወረቀትና ደብዳቤ አይመረመርበትም።

-- ማናቸውም የኢትዮጵያ ተወላጅ፣ በሕግ እንደተጻፈው፣ ለሕዝብ ጥቅም ያስፈልጋል ከሚባልበት ጊዜ በቀር፣ በእጁ ያለውን ንብረቱንና ርስቱን ማንም ሊወስድበት አይችልም።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ የተዘረዘሩትን እነዚህን መሠረታዊ የሆኑትን የሕዝቡን መብት የሚመለከቱትን ጉዳዮች፣ ሕገ መንግሥቱ በግልጽ ቢያቀርበውም፣ በተለይ ኮሎኒያሊስት የሆኑት መንግሥታት (ፈረንሣይ፣ እንግሊዝ፣ ጣልያን) በቁም ነገር አለመመልከታቸው የሚያስደንቅ ሳይሆን አልቀረም። በእነሱ አስተያየት፣ የምክር ቤቱ አባሎች የመንግሥቱን የሥራ አመራር ለመቆጣጠርና በአንዳንዱም ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ፣ በድምፅ ብልጫ ለመፍቀድ ወይም ለመጣል መብት አልተሰጣቸውም በማለት፣ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕገ መንግሥት ምንም ዓይነት ግምት እንዲሰጠው አልፈለጉም።

እርግጥ ! ከሰማንያ ዓመታት በፊት የሰለጠኑት አገሮች የፓርላማ አሠራር እንዴት እንደሆነ፣ የሕዝብ እንደራሴዎችም ኃላፊነት እስከምን ድረስ እንደነበረ ጥናት ሲደረግ፣ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመልካም ፈቃድ ሕገ መንግሥት እጅግ ወደ ኋላ የቀረ መሆኑን የሚክድ የለም። ነገር ግን ቅን በሆነ መንፈስ መታየት ያለበት፣ በዚያን ዘመን ኢትዮጵያ ገና በጭለማው ዓለም ውስጥ የምትገኝ መሆኗን ነው።

ከዛሬ ሰማንያ ዓመታት በፊት በሰለጠኑት የአውሮፓ አገሮች፣ የሚካሄደውን የፓርላማ አሠራር ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በትክክል የሚያውቁ ነበሩ። ፓርላማ፣ መንግሥትን ለማቋቋምና መንግሥትን ተቆጣጥሮ ለመሻር፣ ሥልጣን ያለው መሆኑን በመስማት ብቻ ሳይሆን፣ አውሮፓን በጐበኙበትም ዘመን በዓይናቸው አይተዋል። ይሁን እንጂ፣ ይህን የመሰለውን የፓርላማ አሠራር ቀድቶ የኢትዮጵያ ሕዝብ እንዲጠቀምበት ለማድረግ ጨርሶ እንደማይቻል፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴና

ፕሮግሬሲስቶቹ ረዳቶቻቸው ደህና አድርገው አውቀዋል። ስለዚህም፣ ለሕገ መንግሥቱ አጥኚ ኮሚቴ፣ ንጉሠ ነገሥቱ በሰጡት መምሪያ፣ የሚዘጋጀው የሕግ መወሰኛና የሕግ መምሪያ ምክር ቤቶች ደንብ፣ የኢትዮጵያን ሕዝብ ጥቅም የሚመረኮዝ፣ የኢትዮጵያን መሠረታዊ ባሕልና ወግ የሚከተል፣ መሆን እንዳለበት አጠንክረው ማስገንዘባቸው ይታወሳል።

በሕገ መንግሥቱ ዝግጅት ላይ፣ ከጥንት ሲያያዝ የመጣው ልማዳዊው የአገዛዝ ሥርዓት እንዲቀጥል በሚደግፉት መሳፍንትና፣ ዘመናዊው አስተዳደር እንዲመሠረት በሚፈልጉት ፕሮግሬሲስት በሆኑ ሚኒስትሮች መካከል ያለው የሐሳብ ልዩነት፣ ብዙ ውዝግብ ፈጥሮ እንደነበረ የሚረሣ አይደለም። የሕዝብ እንደራሴዎች ናቸው ተብለው የተመረጡት የመምሪያው ምክር ቤት አባሎች፣ የሕዝቡን መብት በሚመለከቱ ጉዳዮች ላይ ሕግ እንዲደነግግ እያዘጋጁ ንጉሠ ነገሥቱ እንዲያጸድቀው ለማቅረብ ይችላሉ የተባለውን ሐሳብ እንኳ፣ መሳፍንትና መኳንንት አንቀበልም ብለው ምን ያህል እንዳስቸገሩ፣ ቀደም ሲል የተጻፈው የዝግጅቱ ታሪክ ሂደት በትክክል አሳይቷል። እንግዲህ ! የቀረው ቢቀር፣ የሕዝብ ወኪሎች የተባሉት መማክርት፣ የተወከሉለትን ሕዝብ አስተያየት ለመንግሥት ማቅረብ አይፈቀድላቸውም ተብሎ ብርቱ ክርክር በሚደረግበት ዓለም ውስጥ፣ እንዴት ተደርጉና በምንስ መንገድ የምዕራብን ሥልጣኔ የሚከተል ፓርላማ በአገራችን ለመመሥረት ይቻል ነበር ወይ ? የሚል ጥያቄ አቅርቦ ጉዳዩን ማመዛዘን ያስፈልጋል።

ከዛሬ ሰማንያ ዓመታት በፊት አገራችን በምን ሁኔታ ላይ እንደምትገኝና የገዥዎቿም አስተሳሰብ ምን እንደነበረ ለማወቅ ያልቻለ ሰው፣ ይህ የመጀመሪያው ሕገ መንግሥት ምን ያህል ፈተናዎችን አሳልፎ እንደተወለደ ለመረዳት አይችልም። ኢትዮጵያ በታሪኳ ለመጀመሪያ ጊዜ፣ የሠለጠኑትን አገሮች አቅጣጫ በመከተል፣ የሕዝብን አስተዳደር በሚመለከት ጉዳይ፣ የመወሰን መብት ባይኖረው እንኳ፣ ቀስ በቀስ የሚመክርና አስተያየት የሚሰጥ አንድ የሕዝብ አካል መቋቋሙን በቀላሉ መገመት አይገባም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጣት በሚቆጠሩ ጥቂቶች ፕሮግሬሲስት ከሆኑ ረዳቶቻቸው ጋር ሆነው፣ መሳፍንትን በመቋቋም፣ ይህን ሕገ መንግሥት አዘጋጅተው፣ ሐምሌ 9 ቀን 1923 ዓ.ም በይፋ ካፀደቁ በኋላ፣ ጥቅምት 24 ቀን 1924 ዓ.ም በነገሡ ልክ በዓመቱ፣ የመጀመሪያውን ፓርላማ ለመክፈት በመቻላቸው፣ ታሪክ ትክክለኛውን አስተያየት ይነፍጋቸዋል ብለን አናስብም።

# የተክለ ሐዋርያት አስተያየት

ጃንሆይ! " … በራስዎ ፈቃድ ለሕዝብዎ መተዳደሪያና ለመንግሥትዎ አመራር ሕገ መንግሥት ማቆምዎ፤ ለኢትዮጵያ ምን ያህል ውለታ መሆኑን ማንም አይስተውም … "

**ተክለ ሐዋርያት ሐምሌ 9/1923**

ለኢትዮጵያ ሕዝብ መተዳደሪያ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አስበው ስለአወጡት ሕገመንግሥት፤ በዚያን ጊዜ የዝግጅቱ ኮሚቴ አባልና የገንዘብ ሚኒስትር የነበሩት በጅሮንድ ተክለሐዋርያት፤ ለመሳፍንቱና ለመኳንንቱ እንዲሁም የሕዝብ ጉዳይ ኃላፊነት ላላቸው ለመንግሥት ባለሥልጣኖች በሙሉ፤ ትምህርት ነክ የሆነ ሰፊ ማብራሪያ ሰጥተው ነበር። የገንዘብ ሚኒስትሩ ባደረጉት ንግግር ውስጥ፤ ከገለጿቸው ሐሳቦችና መሠረታዊ አስተያየቶች መካከል ዋና ዋናዎቹ ፍሬ ነገሮች የሚከተሉት ናቸው።

- ዘንድሮ በኢትዮጵያ የተፈጸመው ሐሳብና የተወጠነው ዕቀድ፤ በዓለም ላይ <u>በማናቸውም አገር በማናቸውም ጊዜ ተደርጐ የማያውቅ ነው።</u>

- ይህንን ለአገራችን እርምጃ የሚበጀውን ሕገ መንግሥት፤ የእኛ ትውልድ በሚኖርበት ዘመን በመፈጸሙና ለማየትም ለመስማትም ስለበቃን፤ ዕድላችን በከፍተኛ አኳኋን መገመቱ የማይቀር ነው። ወደፊትም መጭውን ትውልድ የሚያስከብር መሆኑን አንጠራጠርም።

- በዚህ ዓለም ላይ ኢትዮጵያ በመንግሥትነት ከታወቀች ከሦስት ሺህ ዘመን ይበልጣል። ከዚያን ጊዜ ጀምሮ እስከዛሬ ድረስ እጆቿን ወደ ሰማይ ዘርግታ ለመተዳደሪያዋ አንድ ችሮታ ለማግኘት በትዕግሥት ስትጠባበቅ ቆይታ ስለነበር፤ ዛሬ የእግዚአብሔር ቡራኬ በግርማዊነትዎ እጅ እንዲደርሳት ዕድል አግኝታለች።

- ፈጣሪያችን መኖሩንና የበላይ ገዥነቱን የሚያሳምነን ዓለምን በሙሉ በጽኑ ሕግ ለዘለዓለም እንዲሠራበት ወስኖ መፍጠሩ ነው። የሰው ልጅም ትልቅነቱ፤ የፈጣሪውን ሕግ እየተመራመረ ትክክለኛውን ትርጉም በመረዳቱና በመከተሉ ነው። ስለዚህም፤ ራሱን ያስከብራል ወገኖቹንም ይጠቅማል። <u>**ጃንሆይ! ለኢትዮጵያ የሚበቃ ውለታ ለመሥራት፤ ሕገ መንግሥት ከማቆም የበለጠ ሌላ ምንም ማድረግ አይቻልም።**</u>

- ለመንግሥት አመራር መሠረት መትከልና የሕግ ምሰሶ ማቆም፤ ለትውልዳችን መጠቀሚያ የሚያስፈልግ ትልቅ ቁም ነገር መሆኑን ግርማዊነትዎ ስለተረዱት፤ እኛም የኢትዮጵያ ተወላጆችና ዜጎችዎ የዚህን ግምት አመዛዝነን ለመረዳትና የሠሩልንን ውለታ ለማወቅ ስለቻልን፤ ድካምዎ ሁሉ ከንቱ አይሆንም።

- እኛ ዛሬ አብረንም የምንኖር ሰዎች፤ ለዚህ ላደረጉልን ወሮታ እንደሚበቃ አድርገን ውለታ መላሽ ለመሆን እናውቅበት ይሆን? ... የዚህስ ውለታ አመላለስ በምን አኳኋን ሲሆን ነው በቂ ነው ማለት የሚቻለው? ለእነዚህ ጥያቄዎች የቃላት መልስ የሚሰጡባቸው አይደሉም። መልሱ፤ ሕገ መንግሥቱ በቸረው መብት በተግባር መገለጽ ያለበት ነው ... "

በጅሮንድ ተክለሐዋርያት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ማንም ሳይጠይቃቸው በራሳቸው ሐሳቢነትና ፍላጐት፤ ለኢትዮጵያ ሕዝብ መተዳደሪያ ይህንን በታሪካችን ለመጀመሪያ ጊዜ የሚቆምልንን ሕገ መንግሥት አዘጋጅተው በመስጠታቸው፤ ከዚህ በላይ እንደተገለጸው የተሰማቸውን አድናቆትና ያደረባቸውን ከፍተኛ ስሜት በመናገር የጋለ ምሥጋናቸውን ለንጉሠ ነገሥቱ ካቀረቡ በኋላ፤

**ልዑላን መሣፍንትና ክቡራን መኳንንት፤**
**ክቡራን ባላባትና ክቡራን ታላላቅ ሰዎች፤**

የዚህን ሕገ መንግሥት ትክክለኛ ትርጉም፤ የሐሳቡን ጥልቀትና መሠረታዊ አቋሙን የሕገ መንግሥቱም ተጠቃሚ ማን መሆኑንና ጥቅሙስ እስከምን ድረስ እንደሆነ፤ የኢትዮጵያም ሕዝብ፤ ይህንን በቅን መንፈስና በሰፊ ችሮታ ታስቦ የተሰጠውን ሕገ መንግሥት በሚገባ ተረድቶ ከተጠቀመበት፤ በየጊዜው ዘመኑ የሚያፈልቀውን ዴሞክራሲ በመከተል፤ ይህ ሕገ መንግሥት እየተሻሻለ መብቱን እያስፋለት የሚቀጥል መሆኑን፤ ትምህርታዊ በሆነ አቀራረብ በሰፊው አስረድተዋል። ከላይ እንደተገለጸው፤ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የገንዘብ ሚኒስቴር፤ በጅሮንድ ተክለሐዋርያት፤ ሕገ መንግሥቱ በሚዘጋጅበት ጊዜ የታላቁ ኮሚቴ አባል በመሆን ከፍተኛ ሚና የተጫወቱ በመሆናቸው፤ አሁንም ሕገ መንግሥቱን በማስተማር ያደረጉት ጥረት እጅግ ከፍ ያለ ነው።*

---

* ቀ.ኃ.ሥ ሕይወቴና የኢትዮጵያ እርምጃ ከገጽ 154-167
ዝክረ ነገር (ማሕተመሥላሴ ወ.መ) ከገጽ 800-831